# ፖለቲካና ፖለቲከኞች

ለትችቱ ከተሰጠ



መልስ ጋር

ከአቤ ጉበኛ



አቤ ጉበኛ

ሴንትራል ማተሚያ ቤት

ዋጋው የኢት. 2.00 ብር



# ፖለቲካና ፖለቲከኞች

ለትችቱ ከተሰጠ መልስ ጋር



ከአቤ ጉበኛ

# ፖለቲካና ፖለቲከኞች

## ለትቺቱ ከተሰጠ መልስ ጋር

ከአቤ ጉበኛ

ሚያዝያ ፲፪ ቀን ፲፱፻፷፬ ዓ.ም.
በሴንትራል ማተሚያ ቤት ታተመ ።

pdf www.binyamkk.wordpress.com



## በመጀመሪያ ቴያትሩን ካሳዩት ብዙዎቹ ተጨዋቾች

| | |
|---|---|
| አበራ ደስታ | እንደ ፕሮፌሰር ተዘራ |
| ጌታመሳይ አበበ | » አቶ ፈረደ |
| ዘነበች ታደሰ | » ወ/ከበደች |
| ግርማዬ መኰንን | » ጋዜጠኛ ጐርፉ |
| አብራር አብዶ | » ዶክተር ምትኩ |
| በላይነሽ አመዴ | » ጋዜጠኛዋ ፀሐይ |
| በቀለ ወ/ጻድቅ | » ሰብሳቢ ዳኛ |
| ግርማ ብሥራት | » የቀኝ ዳኛ |
| ንጉሤ ኃይሉ | » የግራ ዳኛ |
| መኰንን አበበ | » የወህኒ ቤት ሹም |
| ቀለመ ወርቅ ደበበ | » ዐቃቤ ሕግ |
| አስመላሽ ለጋሥ | » ፖሊስ |
| ዓለምዬ መብሬ | » » |
| አዳነ መርስዔ | » ዕብዶች |
| ጌታቸው የሻው | » » |
| ቢተው ወርቁ | » » |
| ባንጋ በጨ | » » |
| ገረሱ ሐንኬ | » ተላላኪ |
| አስፋ ግዛው | » » |
| ኃይሉ ዲሳሳ | » » |
| ካሣሁን አወቀ | » » |

| | |
|---|---|
| ግርማ ፈለቀ | እንደ ተላላኪ |
| ይርሳልኝ ልመንህ | » » |
| የሺ ተክለ ወልድ | እንደ አሻሻጮቹ |
| አልማዝ ቢሆን | » » |
| ዓለምነሽ ወልደ ትንሣኤ | » » |
| ሙዚቃ | ሻለቃ ግርማ ሐድጉ |
| የመድረክ መብራት | ገብረ ኪዳን ደባስና ክፍሉ ክንፉ |
| » ጌጥ | እሼቴ ጥሩነህና ሥዩም አያና |
| የመድረክ ጌጥ አቅራቢዎች | መኰንን ገ/እግዚአብሔር አሰፋ ግዛው ፥ ዓለማየሁ ደስታ ፤ ጥጋቡ ሐዲስ |

ክፍል 1

የወይዘሮ ከበደች ቡና ቤት መኝታ ክፍል

ክፍል 2

ልዩ የዝግ ችሎት ፍርድ ቤት

ክፍል 3

እሥር ቤት

ክፍል 4

የጋዜጠኛው የጉርፉ ቢሮ ።

# መቅድም

ይህ ቴያትር የተጻፈው የምንም ዓይነት ፍልስፍና ማስፋፊያ ወይም መቃወሚያ እንዲሆን ታስቦ አይደለም ። ዋና ዓላማው የሀገራችን ለውጥ ተጀምሮ እየገፋ በመጣበት አንድ ጊዜ ላይ የታየውንና አሁንም በአንዳንድ ሰዎች ላይ የሚታየውን ቅሌትና አሳሳችነት ለሕዝብ ገልጦ ለማሳየትና ፍርዱን ለባለ ጉዳዩ ሕዝብ ለመተው ነው ።

ይህ አባባል የሰውን አእምሮም አካልም በቍጥጥራችን ሥር አድርገን በማንም አናት ላይ እንናጥጥ በሚሉ፤ በጋዜጣና በመጽሔት በጮሁብኝ አንዳንድ ስመ ፡- ማርክሳውያን ዘንድ የሚያስቀጣ ወንጀል ነው ።

ይህ ቴያትር ቀርቦ ከከፍተኛ ስሜትና ደስታ ጋር ሕዝብ በተመለከተው ጊዜ ከእነዚህ ሰዎች አንዳንዶቹ ከግል ትችት አልፈው በጋዜጣ በመጽሔት ወረቀት በመበተን ለማሳጣት ሞክረዋል ። ስሚ ቢያጡ እንጂ "ፀረ—ሶሻሊስት ፀረ—አብዮት አድኅሪ" ሲሉኝ ምን እንዲደረግብኝ መፈለጋቸው ኑሯል?

በነሱ ቤት አንድ ሰው ምንም ያህል ለሀገሩ ጠቃሚ ይሁን ፤ ምንም ያህል ወገኖቹን ይውደድ በነርሱ አስተሳሰብ ካልተስማማ መኖር የማይገባው ሰው ነው ።

ለመሆኑ እነዚህ ጀግኖች እነማን ናቸው ? በልጅነቴ ጊዜ የሚፈሩ ሕፃናት በራሳቸው እንዲቀልዱ ከታላላቅ ዘመዶቻቸውና ጎረቤቶቻቸው የሚነገሯቸው የፉከራ ቃላት ትዝ ይሉኛል ።

"ይኸን ይወዳል ጀግናው .......
የሞት ፈረስ ጋላቢ ፤ የነጠፈ ወሀ ተሻጋሪ ።
አይጥ ሲደነፋ ዘሎ ከቶፋ ! "

እንግዲህ የኛ አዲስ በቀል "ጀግኖች" በግልጽ ለመናገር አንዳንድ የውሸት ተስፈንጣሪ ምሁራን ወይም ምሁራን ፋሽስቶች ይኸን ቀልድ በግብር ያዋሉ ጉዶች ናቸው ።

በራሴ በኩል ለሀገሬ ሠራሁ የሚል እምነት ያለው ሰው እስከዚህ መፎከር አያሻውም ነበር ። ሁኖም 'ድንጋይን ማን ያናግረዋል? ቢሉ ወሀ!' እንደሚባለው አነጋገር እነዚህን ቀላሎች ለማጋለጥ ስል ለመናገር ያልፈለግሁትን ለመናገር ተገደድሁ ። እኔ ለውጥ ሲመጣ ዐይቼ ክንዱ የተጐረደ የካኪ ኮትና ክራቫቱ የተፈታ ሸሚዝ ለብሼ ፈንደል ፈንደል በማለትና ግማሽ ክንዴን ለብርድና ለነፋስ በማጋለጥ ለሀገሬ ከፍተኛ መሥዋዕትነት የፈጸምሁ ጀግና በመምሰል ማንንም ያወናበድሁ ሰው አይደለሁም ።

ሕይወቴ በአምላኬ ኃይል ተጠብቃ እስካሁን ከመቆየቴ በቀር ምኑንም ነገር ሳልቆጠብ ለወገኖቼ ሳበረክት ቆይቻለሁ ። ለውጡ በመጀመሪያ ሲንቀሳቀስ እንዳጋጣሚ ሁኖ እኔም ፈረንጅ አገር ነበርሁ ። ነገር ግን የሀገሬን ችግር ከሩቅ ሁኖ ለማዳመጥ ልብ ስላላገኘሁ የነበረኝን የጉብኝት ጊዜና በዚያ እንድቆይ ካንዳንድ ወዳጆች የቀረበልኝን ጥያቄ እንደሌለ ነገር በመቍጠር ወደ ሀገሬ ተመለስሁ ።

በተመለስሁበት ቀን አንድ ወዳጄ የነበረ አሜሪካዊ ፤ «የሀገራችሁ ችግር ለረጂም ጊዜ የሚቆይ ስለመ



ሰለኝ ቤተ ሰብህንም አውጣና ለሁለት ዓመት ያህል እዚሁ ቆይ » የሚል ሐሳብ አቅርቦልኝ ለሁለት ሰዓት ያህል ስንከራከር ከቆየን በኋላ አንዳንድ ሊያስቈጡት የሚችሉ ቃላት በቀልድ መልክ እየነገርሁት ሳስቈጣውም ሳስቀውም ቆይቼ የአይሮፕላን ትኬትን ወደ ማስመዘግብ በት ቦታ አድርሶኝ ስንሰናበት «መቸገር የማይታክትህ ዕብድ ሰው ነህ» ብሎ እንደ ቀልድ የነገረኝ ነገር አሁንም አልፎ አልፎ ትዝ ይለኛል ።

እንዲሁም በዚያው ሳምንት ውስጥ በዋሽንግተን የነበሩ ኢትዮጵያውያን ተማሪዎች ባደረጉት ስብሰባ ላይ እንድገኝ ጋብዘውኝ በእውነተኛ ወንድማማችነት ስንወያይ ከአንድ ተስፈጣሪ ከሆነ በግምት ከሐያ ዓመት ዕድሜ የማይበልጥ ወጣት ጋር የተለዋወጥሁትን ንግግር እዚህ ላይ ልጠቅሰው እወዳለሁ ።

እሱ ያቀረበው ሐሳብ የኢትዮጵያ ሕዝብ እርስ በርሱ ይፋጅ የሚል ዓይነት ነበር ። እኔ ደግሞ የለም ፤ በረኃብ ያለቀ ችግረኛ ሕዝብ በአካባቢው ብዙ ጠላቶች ያለው ሕዝብ እንዴት እርስ በርሱ ይፋጅ ትላለህ ? ብዬ ምክንያቶቹን በመዘርዘር ነገርሁት ። ከነአካቴውም "ይኸማ ፈሪነት ነው ፤" አለኝና እኔም ፤ "ለመሆኑ ፈሪው ማንኞችን መሆናችን ነው ? እኔን ፈሪ ልትለኝ ፈልገህ እንደሆነ ተሳስተሃል ። ሞትም ይሁን ሕይወት የሀገሬን ሕዝብ ዕድል ለመካፈል መሔዴ ነው ። አንተ ተፋጁ የምትለን ግን ዋሽንግተን ውስጥ በምቾት ቁጭ ብለህ ነው ። እስኪ ደፋር ከሆንህ አብረን ወደአገራችን እንጓዝ ፤» አልሁት ። በዚያ ካየኋቸው ወጣቶች ብዙዎቹ ምራቅ የዋጡና

ጨዋዎች ስለሆኑ ፤ ውይይታችንም በወንድማማችነት ስለ ነበር ሁሉንም በውይይት መንፈስ ተቀብለን በወንድማማችነት መንፈስ ተለያየን ።

ታዲያ በዚህ ሁኔታ ተመልሼ ለውጡን በገለልተኛነት አልተመለከትሁም ። ወገኖቼን ያገለገልሁ በመሰለኝ መንገድ ሁሉ ያለችኝን ዓቅም ወርውሬያለሁ ። ሦስት ውጫጮቼን ለማሳደግ ትረዳኝ የነበረች ሳንቲሜንም አልቆጠብሁ ።

ደግሞ በሌላ በኩል ሁለት ቋንቋዎችን በማጋጨት ለማንም ሊገቡ የማይችሉ ጉድ ቃላትን እየፈጠርሁ ወገኖቼን አላደናገርሁም ።

ነገርን ነገር ያነሣዋልና ፤ ከዚህ ላይ የሕክምናና የባይአሎጂ ሊቃውንት የሚስማሙበትን አንድ «ሳይንሳዊ ሐቅ» ለማውሳት እሻለሁ ።

በተደረገው ጥናት መሠረት ጉድ ልጆች ፤ ማለት የአካሎቻቸው ቅርጾች የተበላሹና የተዘበራረቁ ወይም የጐደሉ ሕፃናት የሚወለዱት አብዛኛውን ጊዜ ከቤተ ዘመድ ጋብቻ ነው ። (የአንዳንድ አገር ሰዎች የአክስት የአጎት ልጅ ያገባሉና በዚህ ዓይነት በሚጋቡ ሰዎች መካከል ይህ ነገር ይበዛል ማለት ነው ።)

የኛ ሊቃውንት ደግሞ ሁለቱን ቤተ–ዘመድ ቋንቋዎች ፤ ግዕዝና አማርኛን እያዳቀሉ የሚፈጥሯቸው ቃላት ለጆሮም ለአእምሮም ጉዶች የሆኑ ማጭበርበሪያዎች ናቸው ።

ይህ ነገር ጠቃሚ ቢመስለኝ እኔም ብገባበት እችል ነበር ። አማርኛ የናት አባቴ ቋንቋ ሲሆን ግዕ



ዝንም የማያልቅበት አምላክ ነፍሶቻቸውን ወደ መንግሥተ ሰማያት ያግባቸውና የኔታ ገሠሠ ፤ የኔታ አክሊሉ በተለይም የኔታ ገሠሠ ከነቅኔው በልጅነቴ አስተምረውኛል ። ግን ስንት ሥራ ሞልቶ የማያስፈልጉ ቃላት ለመፍጠር ሁለት ቋንቋዎች ሲያሣርሩ መዋል በአዲስ ዘመኑ ቋንቋ ለመጠቀም «ከፍተኛ የፖለቲካ አሻጥር» መሰለኝ ።

በራሴ በኩል ተቀዳሚ ሁኖ የታየኝ ሌላ ሌላው ጉዳይ ነው ። በለውጡ መጀመሪያ ሰሞን ከፈጸምኋቸው ሌሎች አገልግሎቶች ሌላ ለዕድገት በኅብረት ዘመቻ ያቀርብኋቸውና ያበረከትኋቸው ሁለት ጠቃሚ ነገሮች ነበሩ ። እነሱም ማንም ሊያስተባብልብኝ የማይችለው የሀገራችንን ፊደሎች እጅግ ቀላልና አጭር በሆነ መንገድ ለማስጠናትና ንባብ ለማስተማር የሚችለው «ንባብ በሰባት ቀን» የተባለው መጽሐፌ ነው ። ሁለተኛው «ደኅና ሁን እንስራ» (ማድጋ ሊባልም ይችላል) ያልሁት የውሀ ማውጫ ማጠራቀሚያና ማከፋፈያ መሣሪያ ነው ።

(እዚህ ላይ የወሀ ማጠራቀሚያውን ዕቃ የሠሩልኝ የብረታ ብረት ሠራተኞችና የድርጅቱ ባለንብረት አቶ ከበደ ካሣዬ ለሥራዬ ካስፈለጉት ዕቃዎች እንዳንዶቹን ተሯሩጠ በማቅረብና ዋጋውንም በመቀነስ የረዱኝ አቶ ግርማ አበበ ሒሳቤን በመደገፍ ፤ ሥራውን በማፋጠንና በዋጋም ባለመጫን ያደረጉልኝን ርዳታ ሳልጠቅሰውና ሳላመሰግናቸው አላልፍም ።)

እነዚህን ሁለት ነገሮች ሠርቼና አሠርቼ ለማቅረብ የነበረኝ የጉልበትና የአእምሮ ድካም ሳይታሰብ በገ

ንዘብ በኩል አራት ሺህ አምስት መቶ ብር አውጥ ቻለሁ ።

ነገሩን በዚህ አላቆምሁም ነበር ። ለምወዳቸው ወገኖቼ በተለይም በገጠር ለሚኖሩት አብዛኛው ሕዝብ በመጽሐፍ ማስተዛዘን ብቻ ሳይሆን ለልማታ ቸውና ለደኅንነታቸው የሚጠቅሙ ብዙ ነገሮች እየሠሩ ለማሳየት በመዘጋጀት ላይ ነኝ ። ነገር ግን ለማዳከም ከሚጣጣሩ ሰዎች በስተቀር ሊረዱኝ የፈለጉ አላገኘ ሁም ። ሁኖም እኔ የማስበው ብዙ ወገኖቼን እንጂ ጥቂቶችን ስላልሆነ የአንዳንድ የዘመኑ ምሁራን ክፋት ሊያዳክመኝ ቀርቶ ስሜት አይሰጠኝም ። ስንት መከራ እያሳለፍሁ የቆየሁት በሕያው አምላክ ኃይልና በሚ በዙት ወገኖቼ ሙሉ አበረታችነት ስለሆነ የጥቂት ሰዎች ጥላቻ ስንት ወገኖቼ ያሳዩኝን ፍቅር ፤ በችግርና በመከራዬ ጊዜም የዋሉልኝን ልባዊ ውለታ ከልቤ ሊፍቀው ቀርቶ ቀለም አይረጭበትም ። አንዳንድ ሳዲ ስቶች (በሰው ሥቃይ የሚደሰቱ ጉዶች) እንደሚመ ኙት ከወገኖቼ በአንዱ እጅ ብሞት እንኳ በዚያ ዕብድ ጭካኔ የብዙዎች ወገኖቼን ቅን መንፈስ ለውጬ አላ የውም ። ያለኝን ያህል ችሎታና ዓቅም ካስፈለገም ሕይ ወቴን ጭምር ለሀገሬ ከማበርከት ከቶውንም ወደ ኋላ አያሰኘኝም ።

«ሴባ እናት ልጅዋን አታምንም» እንደሚባለው መከራችንን ስናይባት በኖርን አገራችን አሁን ዝም ብላችሁ የመቀመጥ መብት የላችሁም የሚሉን በእግራ ቸውም ይሁን በአእምሮዋቸው ሳይሆን በቀጣፊ ምላ ሳቸው የሚራመዱ ውርጋጦቻችን አንድ ኢትዮዮጵ



ያዊ በቅን መንፈስና በወገን ፍቅር ተነሣሥቶ የሚ ሠራውን ነገር ሁሉ እንደነሱ ለጥቅም ሽሚያና ለዝና ብቻ ብሎ የሚሠራው ይመስላቸዋል ።

እንደ እውነቱ ከሆነ ሰው ዝናንም ጥቅምንም አይፈልግም አልልም ። ግን ወገንን መውደድ ደግሞ ከነዚህ ሁሉ በላይ የሚሆንበት ብዙ መንገድ አለ ።

አንድ ሰውዬ ወይም ውርጋጥ ፤ (ይቅርታ መቼም በዓላማቸው ስለማይተማመኑና የራሳቸው ክፉ ኀሊና «ጠማማ ሰው ማንም ሳያበርረው ይሮጣል» እንደሚባ ለው እያሳደዳቸው በአሁኑ ጊዜ ብዙዎቹ ለፍላፊዎች በእውነተኛ ስማቸው ስለማይጽፉ ነው ።) ስለዚህ የቴ ያትር ጽሑፌ ሲተች ጥቅምና ዝና ስለቀረበት በቍጣ ገንፍሎ የጻፈው ነው ፤ የሚል አስተያየት ሰንዝሯል ። ይህም አባባል ከይሉኝታ ቢስ አልፎ ደንቆሮ ሰው መሆ ኑን ያመለክታል ።

ለመሆኑ የቱ ጥቅሜ ነው የተነካው? በየጊዜው መታሠር ጥቅም ነው ? ጐሬና ሞቻ ከሦስት ዓመታት በላይ ታሥሮ በበሽታ ፥ በረኃብ ፤ በግዞት መማቀቅ ጥቅም ነው? ፲፪ ዓመት ሙሉ ያለ ቋሚ ሥራ ዋስትና በሌለው ኑሮ መኖር ጥቅም ነው ? በጠቅላላው ለመግ ለጽ አንድ ሰው የወጣትነት ዘመኑን እንደ አውሬ እየ ታደኑ መኖሩ ጥቅም ነው ? ይኸ ጥቅም መስሎ የሚ ታይህ ውርጋጥ ! ይህ ነገር በጣም አስከፊ መሆኑን ዐይቼ ስለማውቀው ምንም በከንቱ ብትጠላኝ እኔም ባልወድህ እኔን ያጋጠሙኝ ችግሮች እንዲገጥሙህ አልመኝም ። ምክንያቱም ጥቅሞች ሳይሆኑ መከራ ዎች መሆናቸውን ዐውቃለሁ ።

የቀረብኝ ዝናስ የቱ ነው ? ሚኒስትር አምባሳደር ኤክስፐርት ሀብታም ነጋዴ ሁኜ ወይም በቀድሞው የሽልማት ድርጅት የተሸለምሁ ታዋቂ ደራሲ ተብዬ በየሀገሩ መዞር ነው የቀረብኝ ዝና ? አንድ ትንሽ መጽሐፍ ባሳተምሁ ቍጥር ፤ «ቆንጆትዬ! ቅልብጭዬ! መጽሐፍ ናት . . . በውስጧ ባለው ቁምነገር ግን የነሸክስፒዩርን ድራማ የነቶልስቶይንና ዲክሰንን ልብ ወለድ መጽሐፍ የነዳንቴንና የነ ባይረንን ግጥም የምትወዳደር ናት» እያሰኘሁ የምሞገስበት ዝና ነው የቀረብኝ? የቱ ዝና ነው የቀረብኝ ? ዝናን የተራበ ዝናን አያገኝም ። ዝነኛ የሚሆን ሰው የሚሠራውን ነገር ከልቡ አምኖበት የሚሠራ እንጂ ለዝና የሚሯሯጥ አይደለም ። አንድ የሚያስገርም ነገር ልንገርህ ፤ እኔ ለሀገሬ ለፈጸምሁት አገልግሎት ዝና አሠራጭ የሆኑት የዜና ማሰራጫ ድርጅቶች በተለይም ጋዜጦች ማንም አጭበርባሪ ስሙን እየለወጠ እንዲተፋብኝ ከማድረግ በቀር የኔ ዝና ፈጣሪዎች አልነበሩም ። ግን ዝና የሚያስደስት ነገር ከሆነ በዓለም ተበትነው በብዙ ሚሊዮን የሚቈጠር ሕዝብ የሚያነባቸውና በጣም የታመኑ የብዙ አገሮች ጋዜጦች የሕይወት ታሪኬን ግማሽ ወገን እንደ ታላቅ ታሪክ በመቍጠር ሙሉ ገጽ የሰጡት መሆናቸውን በ«ሳይንሳዊ ተጨባጭ ሐቅ» ላረጋግጥልህ እችላለሁ ።

ወገኖቼም ያለምንም አስተዋዋቂ ያውቁኛል ። እጅግ የበዙ የቅርብና የሩቅ ወዳጆችም አሉኝ ። መጽሐፎቼ በብዛት መነበባቸውን እንደሆነ ዝና የምትለው አሁንም በሚገባ ይነበባሉ ። የቴያትሬንም ጉዳይ በዐይንህ በብረቱ ያየኸው ስለሆነ አንተን ያንገበገበውን ያህል



የሰፈውን ከተማ የአዲስ አበባ ሕዝብ ምን ያህል እንዳስደሰተው መንገሩ ለቀባሪ ማርዳት ይሆናል ።

ታዲያ ቀረ የምትለው ዝናዬ የት ላይ ነው ? በኔ አስተያየት የወደቀው መንግሥት ሲያልፍ ያጣሁት ነገር የማያቋርጥ ሥቃይ እንጂ ዝናና ጥቅም አልነበረም ።

ለመሆኑ ከለውጡ በፊት አሁን የሕዝቡ የማንጠየቅ ጠበቆች ነን የሚሉት ሰዎች ስለ ጽሑፎቼ የነበራቸው ትችት ምንድን ነበር? እኔ ስሰማው የኖርሁት ትችታቸው በስድስት ኪሎ ቋንቋ ለመናገር ፤ «የአቤ መጽሐፎች ፤ የሚታየውን የሕዝቡ ችግር እየገለጹ ሕዝብን የሚቀሰቅሱ እንጂ ፕሮፓጋንዳዊ ያልሆነ ኪነታዊ ብፁዓዊ ልዕልናና ጥበባዊ መዋቅረ-ርቀት የላቸውም» የሚል ነበር ።

አሁን ግን የሕዝቡን ችግር የሚመለከት ነገር ከሁሉ ይበልጣል ሲባል የሕዝቡን ችግር አስተጋቢ ሲባል የነበረውን አቤን ፤ «አድኃሪ» በተማሪና በሠራተኛ ስም አሳቦ ሥልጣን ለመያዝ የሚኳትን ዕድል አሳዳጅን «የሰፊው ሕዝብ ሞግዚት» አላችሁ ።

ሌላው ሁሉ ቀርቶ በድሮው በጐ አድራጐት ድርጅት የበላይ ጠባቂነት የተቋቋመቺው «ፀደይ» የተባለች መጽሔት እንኳ እንዳቅሚቲ በተልፈሰፈሰና ግራ በገባው እግሯ ለመራመድ ስትሞክር መርገጥ ባትችልም ጭቃዋን ለመላከክ ቃጥታለች ።

ለመሆኑ በጥፋቴና በስንተቴ ልወቀስ እንጂ ያለ ጥፋቴ ለምን ልወቀስና ልሰደብ? እኔ የቻልሁትን ሁሉ በተረዳሁት መንገድ አበረከትሁ ።

ለውጥ ሲመጣ ዐይቼም እንዲህ ያለ የሹመት ቦታ ይሰጠኝ በማለት ሥራ አላጣበብሁም ።

እዚህ ላይ የራሴን ጉዳይ ገብ አድርጌ ስለሌሎች ሰዎችም በዚህ አጋጣሚ ጥቂት ልናገር ።

ለመሆኑ የነአቶ ሐዲስ ዓለማየሁ ዋጋስ በአንዳንድ አለሁ አለሁ ባዮች መዘርጠጥ ነው? አቶ ሐዲስ ዓለማየሁ «ፍቅር እስከ መቃብር» «ተረት ተረት የመሠረት» «ለኢ. ትዮጵያ ምን ዓይነት አስተዳደር ያስፈልጋታል?» የሚሉ መጻሕፍትን በመጻፍ ብቻ የታወቁ ሰው አይደሉም ። ለሀገራቸው በጦር ሜዳ የተዋጉ ፤ በፋሽስት እጅ ወድቀው ለብዙ ዓመታት የታሠሩ ፤ በተባበሩት መንግሥታት የኢትዮጵያ አምባሳደር ሁነው ሲሠሩ ከመንግሥቱ ዓላማ በማፈንገጥ ለአፍሪቃ ሕዝብ ፍጹም ነፃነት ቅኝ ገዥዎችን የሚያስቈጣና ሌላም ብዙ ሐሳብ እያቀረቡ ሲወቀሱ የነበሩ ፤ በሀገራችን የነበረውን የተበላሸ አስተዳደር በየጊዜው ሲቃወሙ በሀገራቸው ከቆዩበት ጊዜ ይበልጥ በየውጭ አገሩ እንዲኖሩ ተደርገው የቆዩ ፤ በግል ባሕርያቸው ጭምት ትኁትና ሥነ ሥርዓት የጠበቁ ሌሎችም የሚያስመሰግኗቸው ብዙ ባሕርያት ያሏቸው ሰው ናቸው።

ታዲያ አሁን እርፈው በሀገራቸው በተቀመጡበት የሽምግልና ዘመናቸው ማንም እየተነሣ በሽበታቸው ላይ ልፈነጭባቸው ማለቱ ምን ይባላል? ዕብደት ወይስ ጤንነት? በራሴ በኩል የለየለት ዕብደት መሆኑን ሳልገልጽ አላልፍም። ፕሮፌሰር መስፍን ወልደ ማርያምስ ሀገርህን ለምን ወደድህ በመባል እስከዚህ መዘንጣጠል ይገባቸዋል? በርሳቸው በኩል ተደጋግመው ከቀረቡባቸው ክሶች አንዱ አውራጃ ገዥ ተብለው ተሹመው የነበሩ መሆኑ ነው ።



ለመሆኑ መስፍን ወልደማርያም የተሾሙት ለዚያ ሥራ በመጓጓት በደጅ ጥናት የሰውን ጫማ በከንፈራቸው ሲወለውሉ ስለ ኖሩ ነው? የለም ይህ ፍጹም «ኢሳይንሳዊ የሆነ ፀረ — መልካም ኢትዮጵያውያን ውዥንብር» ነው ። የርሳቸው አውራጃ ገዢነት ከእኔው ጐሬ መላክ በመጠኑ ሻል ያለ ግዞት እንጂ ሹመት እንዳልነበረ እናውቅላቸዋለን ። አሁን የሀገራቸውን ጠባይና ባሕል ፈጽመው በማቃውቁ ሰዎች የሚዘለፉትም ሀገራቸውን ስላወቁና ስለወደዱ ነው ።

አሁን ወደ ጉዳዬ ልመለስ ።

ለመሆኑ ኢትዮጵያ ከምን ላይ ነው ያለች ? የቆየችበት ሁኔታስ? የወደፊት ዕድሏስ ? ይኸን ጥያቄ ሲመልሱ በቂ መረጃ ለማቅረብ የውጭ አገሮችን ታሪክ ብቻ የሚጠቅሱ ሰዎች ፡ ማንም በከንቱ ስሙን እየጠራ የሚጐትተውን ታላቁን ሰው ሟቹን ሊቀመንበር ማኦን መጥቀስ ልማዳቸው ነው ። እሱ ባያምንበትም እኔ አማኝ ነኝ ፤ በሰማይ ነፍሱን ይማራትና ! ማርክሲስት ሌኒኒስት ነኝ የሚል ብቻ ሳይሆን የሀገሩን ሕዝብ ችግር በትክክል የተረዳ ራሱን ለሀገሩ ሕዝብ ደኅንነት የሰጠ በሥራው የምወደውና እጅግ የማከብረው ማኦ.ኢስት ነኝ ካለማለቴ በቀር በሰው ደረጃ ከልብ የማደንቀው ሊቀመንበር ማኦ ለሀገሩ ቅሌታሞች ከሰጣቸው ብዙ ምክሮች ጥቂት ዐረፍተ ነገሮችን ልጠቅስ እወዳለሁ ። «መጽሐፍ ማምለክን ተቃወሙ ።» በሰበቡ ብዙ እንድታነቡ እዚህ ላይ ለቁንጽል ጥቅስ የሚያገለግል ብዙ ቃል አላቀርብላችሁም ። (ሳታምኑ ለተጠመቃችሁት ማለቴ ነው ።)

እኔም የምለው መጽሐፍ ሳታመልኩ የሀገራች ሁን ሁኔታ በጤነኛ ዓይን ተመልከቱ ነው ። ለመ ሆኑ የኢትዮጵያ ለውጥ እንዴት መጣ ? በርግጥ ስን ነጋገር ለውጡ ከሚባለው ለየት ያለ መልክ አለው ።

አሁንም እኔ እውነት ብነግራችሁም ፈረንጅ ወይም እስያዊ ስላይደለሁ እናንተም "የጥቁር ጭንቅ ላት ከፍተኛ ነገር ማሰብ አይችልም ።" በሚለው የኢም ፔሪያሊስት ጠበል የተጠመቃችሁ የአፍ ፀረ — ኢም ፔሪያሊስት ስለ ሆናችሁ ጤፍ እንጀራ በዶሮ ወጥ እንዴት እንደሚጐረስ እንኳ አጨመላልቀን በመተር ጐምም ቢሆን ከውጭ መጥቀስ ስላለብን ሊቀ መን በር ማኦን እጠቅሳለሁ ። «አንድን ነገር መርምረህ ካልተረዳህ በቀር ስለዚህ ጉዳይ የመናገር መብትህን ትነፈጋለህ ። ይህ አባባል እጅግ ሸካራ አይደለም? የአንድን ችግር ሁኔታ አሁን ያሉትን ተጨባጭ ነገ ሮች የሱን ያለፈ ታሪክ የሱን መሠረታውያን ምክን ያቶች ሳትረዳ የምትናገረው ሁሉ ምንም ነገር ስለርሱ ተናገር ትርኪ ምርኪ ይሆናል ። ማንም ሰው እንደሚ ያውቀው ትርኪ ምርኪ ነገሮችን መናገር ችግርን አይ ፈታም ። ታዲያ እናንተን (ትርኪ ምርኪ የምትናገሩ ትን ማለቱ ነው ፤) የመናገር መብታችሁን መንፈግ ለምን ትክክለኛ ፍትሕ አይሆንም ?. . . . . . .—. . .

«አንድን ችግር መርምሮ መረዳት ችግሩን ለመፍ ታት ያስችላል ። . . . .

«መጽሐፍ ማምለክን ተቃውሙ ።»

«በመጽሐፍ ውስጥ የተጻፈው ሁሉ ትክክለኛ ነገር ነው ፤ ይህ አስተያየት እስካሁን ወደ ኋላ በቀሩ የቻይና ገበሬዎች ዘንድ አለ ። (፲፱፻፷ ዓ. ም ።) የሚ



ገርመው በኮሚኒስት ፓርቲው ውስጥ እንኳ ሁልጊዜ በውይይት ላይ ፤ «ይህ ነገር በመጽሐፉ ውስጥ የት ላይ እንዳለ አሳዩን» የሚሉ ሰዎች አሉ ። ( ፲፱፻፷ ዓ ም ።) ማኦ ይኸን ስለ ሚመለከት ጉዳይ ብዙ ተናግሯል ። ታዲያ ከኛ አስመሳይ ኮሚኒስቶች አንዳንዶቹ እንዳላነበ ቡት ያነበቡትም እንደዘነጉት እርግጠኛ ነኝ ።

ለመሆኑ የእኛ ለውጥ እንዴት መጣ ? መነሻውስ ምን ነበር ? አንቀሳቃሹ ኃይልስ ? ከለውጡ በኋላስ ምን ሆነ ? አሁንስ እምን ላይ አለን ? የምንጓዘውስ ወዴት ነው ? እነዚህ ጥያቄዎች የውጭ መጽሐፍ አንብቦ በመ ገልበጥ ብቻ የሚፈቱ አይደሉም ።

በዚህ መሠረት ነገሩን ስንመረምረው አስቀድሞ ኢትዮጵያ ከለውጡ በፊት እንዴት ነበረች ? ወደሚለው ጥያቄ ይመራናል። ኢትዮጵያ ከዓለም አገሮች አንዷ መሆ ኗን ሳንክድ የተለየ ጠቅላላ ሁኔታ ያላት አገርም ሁና እናገኛታለን ። ይኸን ሁኔታ ዘርዝሮ ማስረዳቱ ራሱ ታላቅ መጽሐፍ የሚወጣው ስለሆነ የባሕሉንና የታሪኩን ክፍል ለጊዜው ትቼ ባጠቃላይ ለመግለጽ እወዳለሁ ።

የኢትዮጵያ ሕዝብ እንደ ብዙ አገሮች ሕዝብ ሁሉ ብዙ ነገዶችና ጐሳዎች አሉበት ። እነዚህ ነገዶችም በሀ ገሪቱ ልዩ ልዩ ክፍሎች የሚኖሩ ሲሆኑ የአኗኗራቸው ሥርዓትም የተራራቀ ነው ። አብዛኛውን ጊዜ በኢትዮ ጵያ ቈላዎች የሚኖሩት ሻንቅሎች የሚገኙበት የኑሮ ሁኔታ በግዙፍ ሥልጣኔ አንጻር ሲታይ እጅግ ወደኋላ የቀረ ነው ። ሌላው ቀርቶ ብዙዎቹ ከልብስ ጋር እንኳ አይተዋወቁም ። የሰው ሥልጣኔ ከሠራቸው ነገሮች እንደ ጦር ጠመንጃ ካሉት መጋደያ መሣሪያዎችና ሌሎች

አንዳንድ ነገሮች በቀር የደረሳቸው ሌላ ነገር የለም ። ብዙው የኑሮ ሁኔታቸው «የኋለኛው ክፍለ ጊዜ የድንጋይ ዘመን» እየተባለ በታሪክ በሚነገረው ክፍለ ጊዜ ነበሩ ከሚባሉት ሰዎች የኑሮ ሁኔታ አለፍ የሚለው በከፊል ነው ። ዕድል አጋጥሟቸው የትምህርት ጮራ ያገኙትን አንዳንድ ሰዎች አይጨምርም ። ሌላው የሕዝቡ ክፍል የከብቶቹን ጅራት ተከትሎ የሚዞረው መኖሪያ ቤቱ የጠራ ወሀ የለመለመ ሳር ያለበት አካባቢ ሁሉ የሆነው ዘላኑ ክፍል ነው ።

ከዚያ ቀጥሎ ገበሬው ክፍል ይገኛል ። ይኸ ክፍል ከሌሎች በብዙ መንገዶች ይበልጣል ። ከጠቅላላው ሕዝብ እጅግ የሚበልጥ ቍጥር ያለው እርሱ ነው ። የርሻንና የርቢን ሥራ አጣምሮ ይሠራል ። ቋሚ ጐጆ አለው ። ኑሮውን ለማሻሻልም ከሌሎች ይበልጥ ይጥራል ። ከዚያ በኋላ ከተሜውና ፊደል ቀመሱ ይመጣል ። ይህ ክፍል ከዘመኑ ሥልጣኔ ፍሬዎች ብዙዎችን የመቅመስ ዕድል ቢያገኝም ቍጥሩ በጣም ትንሽ ነው ።

እንግዲህ እነዚህ ክፍሎች በየበኩላቸው የሚያከብሩትና የሚጸየፉት የሚወዱትና የሚጠሉት የሚሞቱለትና የሚገድሉበት ባሕል ልማድና እምነት አላቸው ። ታዲያ በዚህ ዓይነት ሁኔታ የሚገኘውን ሕዝብ ባጠቃላይ የሚመለከት ለውጥ እንዴት ሊመጣ ቻለ? እርግጥ ፤ ባለፈው አስተዳደር መበላሸት ምክንያት በየትኛውም ቦታ ከማንኛውም ወገን ያለው ሁሉ ጭቆናው ተሰምቶት ነበር ።

የአስተዳደሩና የፍርዱ ሥራ መጨማለቅ የጉቦውና የመጉላላቱ ብዛት ግብር እየከፈሉ ከፍትሕ ጀምሮ



ምንም ዕድገት አለማግኘት ለአብዛኛው ክፍል ተሰምቶት ከመሰልቸት አልፎ ከመቆጨት ደርሶ ነበር ።

ከተሜውም ብዙ ጥላቻ አድሮበት ነበር ። ከዚህ ሌላ ፊደል የቈጠረው ክፍል አብዛኛውንም ተማሪው ያን መንግሥት በየጊዜው በግልጽ ይቃወም ጀመር ። የነታኅሣስ አምስት አምሳ ሦስት ዓ. ም. የመንግሥት ግልበጣ ሙከራም ምንም እንኳ ቢከሽፍ ትቶት የሔደ ቅሪት ነበረው ። ውስጥ ውስጡን እየተጠነሰሱ የከሸፉ ብዙ ሴራዎችም የወሬ መነቃቃትን ሳይሰጡ አላለፉም ። በብዙ ክፍላተ ሀገሮችም ከፍተኛ ተቃውሞዎች ታይተዋል ። ለነዚህና ለቀሩት ተቃውሞዎች ሁሉ የየራሳቸው ምክንያቶች ነበሯቸው ።

ሁኖም ለሁሉም ማጠቃለያ የሆነው የየካቲት ወር ፷፮ ዓ. ም. ንቅናቄ በታክሲ ነጂዎች ተጀምሮ ወደፊት ሊገፋ የቻለው ወታደሩ ክፍል ስለተንቀሳቀና ጠቅላላው ሕዝብ ከልብ ስለ ተባበረ ነው ።

ነገር ግን ለውጡ ገፍቶ ካንድ ደረጃ ላይ በደረሰበት ጊዜ በዚህ የቴያትር ጽሑፌ እንደገለጽኋቸው ያሉ «ጀግኖች» ብቅ ብቅ አሉ ። ብቅ ብለውም አልቀሩ ፤ ለውጡን የመራውን ወታደራዊ ክፍልም ሆነ ሕዝቡን የለውጡ ባይታዎር አድርገው «ለውጡ የመጣው በኛ ታሪካዊ ትግል ብቻ ነው» አሉ ። ዋሹ ፤ አወናበዱ ። አሁንም አይጠፉም ። እነሱ እንዳሻቸው ይሁኑ ። አሁን ችግር የሆነብን በሀገራችን ሁኔታዎች ላይ የምንመለከታቸውን ችግሮች እንዳንወያይባቸው ለምን ትንፍሽ ብላችሁ ማለታቸው ነው ። ለመሆኑ እነ ግርማዊ ጭጭ ይበሉና እነ አፈ–ንጉሥ አይተንፍሱ እንደሚመኙት ሁሉ ሥልጣን

የነሱ ቢሆን ኖሮ ምን ሊሠሩን ኑሯል ? ለነፃነት ለእኩልነትና ለፍትሕ ስንታገል ኖርን የሚሉ ሰዎች ለምን ሐሳብን በመጨቆን ያምናሉ? ጥቅምን ሲያሳድዱ ሊደርስ የሚችለውን የማይጠገን አደጋ እያዩስ እነሱም ለምን ይታወራሉ ? እኔ ግን ማንም ዋሾ ይጥላኝ እንጂ ያየሁትን መግለጤን መተውን እንደከፍተኛ ሀገርን መካድ ስለምቈጥረው ያየሁትን እውነት በቀልድ መልክ አቅርቤላችኋለሁ ።

አቤ ጉበኛ





# ክፍል ፩ ።

## ትርእይት ፩ ።

ጊዜው ከጠዋቱ አንድ ሰዓት ተኩል ነው ። ቦታው ደጃች ውቤ ሰፈር የሚገኝ የአንድ ሴተኛ አዳሪ «ግሮሰሪ» የሚባል መጠጥ ቤት የተለየ ስፍራው የቡና ቤቱ ባለቤት የወይዘሮ ከበደች መኝታ ክፍል ነው ። ተዘራ ልብሱን ለብሶ ካልጋው ጥግ ቁሞ የሱሪውን ቁልፍ እያጠባበቀ ከፍርሃት ጋር ሲንጐራደድ ወይዘሮ ከበደች ባልጋው ላይ እንደተጋደመች አንገቷን ካንሶላውና ከብርድ ልብሱ ወጣ አድርጋ ትመለከተዋለች ።

ተዘራ — አዬ አምላኬ ፡ አሁን ምን ሠራሁህ? አዬ መከራዬ! ምነው እናቴ ጥንቱን ባልፈጠረችኝ ! (ፊቱን በመረረ ኃዘን ኮስተር አድርጎ ወደ ከበደች ይዞራል) ፍቅርዬ! አለቀ ፤ በቃ! ቢገድሉኝ እንኳ መልካም ነበር ።

ከበደች — ከሞት በላይማ! ምን ያመጡብኻል ?

ተዘራ — በቃ ያንከላሹኛል ። እንደ ፍየል ፡ ጠቦት ፡ በቀላሉ በጠርሙስ በፊያሾኮ ከዚያ በኋላ ያንቺናኔ ነገር አበቃ! ሞት ዐይሻልም ? (ዓይኖቹን በጆቹ ጨፍኖ ለማልቀስ ይቃጣዋል ።) እህ ! ወይኔ !

ከበደች — እንዴ ምን መሆንህ ነው? ወንድ አይደለ ህም እንዴ?

ተዘራ — ምኑን ወንድ ሆንሁት ? እንደ ፍየል ፤ እንደ በግ ግልገል ስንኮላሽ በምኑ ወንድ ሆንሁት ?

ከበደች — እንዲህ ስትፈራ ምን አናገረህ ?

ተዘራ — የኳስ ፍቅርና ስካር ። ፖለቲካማ ታዲያ መች ስወድ ዐይተሽኝ ታውቂያለሽ ?

ካንቺ ይበልጥ የሚያውቀኝ የለም ። ለኋላም ምስክሬ አንቺ ነሽ !

ከበደች — (በፍርሃትና በቊጣ ከወገቧ በላይ ካልጋው ቀና ብላ) እንዴ ! ምን ነካህ! በዚህ ጣጣ ደሞ ልትጐትተኝ ፈለግህ?

ተዘራ — (ትኩር ብሎ እየተመለከታት) ኧረ ታዘብ ብሁሽ ! ታዲያ ዊስኪ ለመጋበዝና ወደ አልጋ ስጐትትሽ ብቻ ነው ደስ የሚልሽ?

ከበደች — (በግድ ሳቅ ትልና) እኔ ያልኩህኮ ! . . . . .

ተዘራ — አንቺ ያልሽኝኮ ! (ወደ አልጋው ጠጋ ብሎ ጐንበስ ይልና ይመለከታታል ።) እኮ ፤ አንቺ ያልሽኝ እኮ ?

ከበደች — በቃ ፤ ለምስክርነት እንዳትጠራኝ ነው ።

ተዘራ — አዎ ! መስሎሻል ። እንኳን አንቺ አሻሻጮችሽ አይቀሩም ።



ከበደች — እኔ ምን ቸገረኝ ? ሲሳደብ ስምቻለሁ እል ልኻለሁ !

ተዘራ — ማንን?

ከበደች — እሱን ፤ የሰደብሽውን?

ተዘራ — አንቺም ፖለቲካ ገባሽ ! (ወደበሩ ይዞርና ለባዶው ቦታ ድምፁን ጥቂት ከፍ አድርጎ) ልብ አድርጉ ፤ ጌቶችን አንተ ስትል ! (ወደ ከበደች እንደ ገና ይዞራል) የሰደብ ሽውን ? ጃንሆይን አንተ ትያለሽ ? በቃሽ፤ አንቺም ገባሻት! የሚንኮላሽ ነገር ባይኖርሽም አንቺም ትቀምሻታለሽ ! በቃ ! አለቀልሽ ! የሰደብሽውን ? ጃንሆይን አንተ ትያለሽ?

ከበደች — ሆ ! ሆ! «የአቦን ፍየል የበላ ምላስ ይለፈል ፋል ቢሉት ይኸው እኔ በልቻለሁ ። ግን መቼ ለፈለፍሁ ?» አለ የሚባለው ነገር ደረ ሰብህ ።

ተዘራ — እሱን ተዪውና አሁን ምን አድርግ ነው የምትዪኝ?

ከበደች — ምን ልበልህ ?

ተዘራ — ሴት መላ ያውቃል ይባላል ፤ ምን መላ ትመ ክሪኛለሽ?

ከበደች — ለዚህ ምን መላ አለው ? መላው ቀድሞ ቀረ !

ተዘራ — መቼ ?

ከበደች ስክረህ ሳትቀባጥር ።

ተዘራ (ቈጣ ብሎ ) ለማን ስል ሰከርሁ?

ከበደች ለራስህ !

ተዘራ ለራሴ?

ከበደች እሺ ! ለኳስ ?

ተዘራ (ይበልጥ ቈጣ ብሎ) ለኳስ?

ከበደች (ፒጃማዋን ብቻ እንደለበሰች ብድግ ብላ ተነሥታ ወደ ተዘራ እየተጠጋች) ለማን ልበልህ ? ላገርህ?

ተዘራ (በረድ ብሎ) ላንቺ አይደለም?

ከበደች ምን ያልኸው?

ተዘራ የምቀመቅመው ፣ የማቀመቅምሽ?

ከበደች እሱን ተወው !

ተዘራ (የትዝታን ዜማ በቀልድ እያበላሸና እየተወዛወዘ) «ቀምቅሜ ቀምቅሜ ካላቀመቀም ኋት ፣ ታባርረኛለች እኔ መች አጣኋት! » ሲል ተጫዋቹ የዘፈነውን ታውቂውየል ?

ከበደች ወይ ጣጣ ! (በረድ ብላ ካልጋው ላይ ትቀመጣለች ።)

ተዘራ (ተከዝ ብሎ መሬት መሬቱን ሲመለከት ይቆይና) ጉድ! ጉድ! እስኪ ምን አገባኝ? ኳስ ቢገባ ባይገባ ! የኢትዮጵያ ቡድን ቢያ



ሸንፍ የሳንቶስ ፤ የቶማስ ቢያገባ የመር ቆሬዎስ እኔን ምን አገባኝ? ደሞስ ንጉሥ ወርቅ ቢሰርቅ ብር ምን አገባኝ ?

ከበደች እንግዲህ ካፍ ያመለጠ ነገር ተመልሶ አይገባ !

ተዘራ ለመሆኑ ያ ጆሮ-ጠቢ የሚረሳው አይመስልሽም?

ከበደች ከፊትህ ላይ በማስታወሻው ሲጽፈው እያየህ እንዴት ይረሳዋል ብለህ ታስባለህ?

ተዘራ ጻፈው እንዴ ? እኔ እኮ አላየሁትም ።

ከበደች እንደዚያ ዛዝተህ ምኑን ታውቀዋለህ?

ተዘራ ለመሆኑ በትክክል ያልሁት ምንድን ነበር ?

ከበደች ምኑ ቅጡ!

ተዘራ እንዲያው አንዳንዱን እስኪ ንገሪኝ ።

ከበደች ኧረ ምኑን ይዤው ! እሱ ካልሞተ በኳስ አናሸንፍም ። እኛ የኳስ ጨዋታ ማደርጃ ተቸግረን እሱ መዓት ብር ወደ ፈረንጅ አገር ይልካል ትል ነበር ።

ተዘራ ማንን ነው እንደዚያ ያልሁ ?

ከበደች ጆከር ፤ ቅብጥሶ ትል ነበር ።

ተዘራ አልሁ?

ከበደች ኧረ ይኸ ጨቋኝ ንጉሥም ብለኸል ።

ተዘራ እውነትሽን ነው ?

ከበደች አዎ ።

ተዘራ አሁን እንደዚህ ብለሽ ትመሰክሪብኛለሽ?

ከበደች ወድጄ !

ተዘራ አዬ መከራዬ !

ከበደች እንግዲህ ባፍህ ያመጣኸውን መቀበል ነዋ!

ተዘራ አፌን ቢቀጡትማ ደግ ነበር ። 'አይጥ በበላ ዳዋ በዱላ' እንደሚባለው (ወደ ጣብቂያው . . . እያመለከተ) እነሱ የሚቀጡት ሌላውን አካል ነው አሉ ። (ከመኝታው ክፍል የሚቀጥለው በር ይንኳኳል ። ከበደች ከተቀመጠችበት ትነሣለች ። ተዘራ ጉልበቶቿን በሁለት እጆቹ ጨምደድ አድርጎ በሹክሹክታ) በእመቤቱ ማርያም ! በጭንቅ አማላጅዋ! በምታምኚው በቁልቢው ገብርኤል ብለሽ አትክፈቺው ።

ከበደች (እሷም በሹክሹክታ) ታዲያ ምን ላድርግ?

ተዘራ ዝም ብለሽ ቆዩ ።

ከበደች ለምን?

ተዘራ ፖሊሶች ናቸው ።

ከበደች እንዴት ዐወቅህ ?

ተዘራ አትጠራጠሪ ፤ እነሱ ናቸው ። (በሩ እንደገና ይንኳኳል ። ተዘራ ይብሱን



ድምፁን ዝቅ አድርጎ ግንባሩን ወደጫማዎቿ እያወረደ) ስለነፍስ አትክፈቺው ።

ከበደች (ግራ ገብቷት) እኮ! ታዲያ ምን ላድርግ ?

ተዘራ በፊት ደብቂኝ ።

ከበደች እምኑ ውስጥ ልደብቅህ ? በቀሚሴ ውስጥ አልደብቅህ በጣም ትልቅ ነህ ።

ተዘራ አንቺ ትቀልጃለሽ ። ለምን በቁም ሳጥኑ ውስጥ አትደብቂኝም ?

ከበደች የት ይችልኻል ?

ተዘራ (እየተርበተበተ) እሺ ፤ ባልጋው ሥር ልደበቅ ።

ከበደች ድንገት ጠርጥረው የፈተሹና ያገኙህ እንደሆነስ ? እኔም አብሬ ልሠቃይ?
(በሩ እንደገና ሲንኳኳ ተዘራ ሌላ ፈቃድ ሳይጠይቅ ወደ ፋሚሊው አልጋ ሥር ይሻጣል ። ከበደች የአልጋውን ልብስ ወደታች ዘርጋ ዘርጋ ካደረገች በኋላ በሩን ትከፍትና ወደሌላ በር ትጠጋለች ። )
ማነህ ?

አልማዝ (ከውጭ በቀጭን ድምፅ) እትዬ እኔ ነኝ።

ከበደች ማነሽ ? አልማዝ ነሽ ?

አልማዝ አዎ ፤ እኔ ነኝ ።

ከበደች ምነው ሳይነጋ ? ባለወተቱ መጣ እንዴ ?

አልማዝ የቱ ባለወተት ?

ከበደች ኡህ ! ሰው የለም ወይ?

አልማዝ የምን ሰው ?

ከበደች (በቁጣ) ሰው አልመጣም ወይ ?

አልማዝ ኸረ የለም!

ከበደች ታዲያ ሳይነጋ ምን ትረብሽኛለሽ ?

አልማዝ እትዬ አልረበሽኩም እኮ !

ከበደች ታዲያ ምን ማድረግሽ ነው ?

አልማዝ ወህውን አሙቀሽ ጠዋት ቀስቅሽኝ አላሉም ነበር?

ከበደች እ ! እሱን ነው ? ተዪው ይቆይ ።

አልማዝ እሺ ።

(ከበደች ወደ መኝታ ክፍሏ ትመለሳለች ።)

ከበደች ትሰማለህ ?

ተዘራ (ካልጋው ሥር እንዳለ በቀስታ) እ !

ከበደች ውጣ ማንም አልመጣ ።

ተዘራ እ!

ከበደች (ድምጿን ከቅድሙ ከፍ አድርጋ) ውጣ ማንም የለ ! ኡህ ! ምን ዕዳ ነው እቴ!
(ተዘራ ካልጋው ሥር ይወጣል ።)

ተዘራ ምን አድርግ ትይኛለሽ ? ሥቃይ መግባቴኮ ነው ።

ከበደች ይህን ያህል ስትፈራ ምን ያስቀባጥርኻል ?



ተዘራ ኳስ ! ኳስ እያለ ምን ጤና አገኛለሁ ! ገና ይዞኝ ወደ ገሐነም ሳይወርድ ይቀራል? ኳስ የሚሉት በሽታ የኳስ ቲፎዞነት አበሳጨኝ ፤ አሰከረኝ ፤ አናገረኝ ፤ ገና ደግሞ ያስገርፈኛል ።

ከበደች በቃ እንግዲህ እንደ አመጣጡ ተቀበለው ።

ተዘራ መንከላሸቱንም?

ከበደች (እንደ መሳቅ ብላ) እሱ እንዳለ የት አየህ?

ተዘራ ሲሉ ሰማሁ ።

ከበደች ታዲያ ለወሬ ነው እንዴ ይህን ያህል ሽብር?

ተዘራ ክፉ ወሬ ነውኮ ከብዬ !

ከበደች (በመሰልቸት) እሺ ይሁን ፤ በል አሁን እዚሁ እንዳይዞህ ወጣ በልና ተደብቀህ ለማረሳሳት ሞክር ።

ተዘራ የት አባቴ ልግባ ? የማማን ቤትም የኔን ቤትም ወዲያው ያገኙታል ።

ከበደች ለምን ወደ ገጠር ወጣ ብለህ አትቆይም ?

ተዘራ ከዚያስ ቢሆን የት ያጡኛል ።

ከበደች እስከዚህ የሚያሳድዱህ ነፍስ ገድለኻል እንዴ?

ተዘራ ነፍስ ብገድልማ! በማን ዕድሌ ከነፍስ ግዳይ በንጉሡ ላይ አንዲት ክፉ ቃል መናገር እጅግ እንደሚከብድ አታውቂም ?

ከበደች ታዲያ ምን ይሻልኻል ?

ተዘራ እስኪ አንድዬ ይሁነኝ ! በይ ደኅና ሁኝ ! መቼም እንግዲህ መልሰን እንተያይም !

ከበደች — አይዞህ እንጂ ። የታሠረም ይፈታልኮ ።

ተዘራ — ሞክተው ቢፈቱኝ ምን ዋጋ አለው?

ከበደች — አይዞህ ።

ተዘራ — በይ ደኅና ሁኚ !

(ጉንጬን ስሞ ይሰናበታትና ይወጣል ። ከበደች ጥቂት ተከዝ ብላ ትቆይና ወደ በሩ ትሔዳለች ።)

ከበደች — (ከፍ ባለ ድምፅ) አልማዝ ! (ጥቂት ቀስ ብላ) አልማዝ !

አልማዝ — (ከውጭ) አቤት ።

ከበደች — ቡና አላፈላችሁም ?

አልማዝ — ተፈልቷል ።

ከበደች — እሺ ፤ ልጆችንም ጥሪና ይዛችሁ ፤ ኑ !

አልማዝ — እሺ ።

(ከበደች ተመልሳ ካልጋው ላይ ትቀመጣለች ።

ከጥቂት ጊዜ በኋላ አልማዝ ሲኒዎችን በማስቀመጫው ላይ ደርድራ ታመጣና ካስቀመጠች በኋላ ትወጣለች ። ከዚያም ባንድ እጅዋ እምባበ ቆሎ ባንድ እጅዋ ቡናና ጀበና ይዛ ስትገባ አስቴርና ፀሐይ ተከትለዋት ይገባሉ ። አስቴር ጠጅ ሣርና ነጭ ሪያ ይዛለች ።)



አስቴር — (ለከበደች) እንዴት አደርሽ እትዬ ? ቶሎ መነሣት አቅቶኝ የቡና ተራዬን አልማዝ ወሰደችብኝ ።

ከበደች — (እየሳቀች) አልለቅሽ አለ እንዴ ?

አስቴር — (እሷም እየተሽኮረመመች) እሱም አይደል ።

ከበደች — ታዲያ ምን ሆንሽ?

አስቴር — እንቅልፉ ተጫጭኖኝ ነው ።

ከበደች — በይ ተዪው አምልጦሻል ።

(አስቴርና ፀሐይ በክፍሉ ውስጥ ባሉት ወንበሮች ላይ ይቀመጣሉ ። አልማዝ በአንድ ደረቅ ወንበር ላይ ተቀምጣ ቡናውን ትቀዳና በፊት ቆሎውን ለከበደች ታቀርባለች ። ከበደች ከቆሎው ችርፍሳ ወደ በራፉ ከበተነች በኋላ ለራሷ አፍሳ መቆረጣጠም ትጀምራለች ። ከዚያ ሁሉም ከቆሎው ከዘጋገኑ በኋላ ቡና መጠጣታቸውን ይቀጥላሉ ።)

አስቴር — እትዬ! ትናንት ጋሼ ተዘራን ምን ነካቸው?

ከበደች — ኤጭ ! በቅቧቃ! ኳስ ኳስ የሚለው ቋንቋ አለው ። አዳሜን የየቤቱ ችግር አስጨንቆ ታል የደላው ሙቅ ያኝካል ፤ እሱ በኳስ ከተሸነፍን ዓለም ትለፍ ይላል ።

አስቴር — ለመሆኑ ሥራቸው ምንድን ነው ?

ከበደች — እናት አባቱ የትም ሰብስበው ያደለቡትን ሀብት እየዘራ መዋል ነዋ !

አስቴር ተዘራ የተባሉት ለዚህ ነው?
(ሁሉም ይስቃሉ ። )

ከበደች አሁንማ ምኑን ተዘራው ! በምስማር ምላጭ በደረቁ ተላጭቶ ከርሸሌው ይወርዳታል ።

ፀሐይ ብዙ ጊዜ ያሥሯቸው ይሆን ?

ከበደች መጠርጠሩስ !

ፀሐይ እስኪ ምን አስለፈለፋቸው ?

ከበደች እባክሽ ተዪው ፤ ጉረኛ ቀባጣሪ ነው ። የናቱን ያባቱን ሀብት እየቈጠረ መቀባጠር መሰለውና በወጥመድ ገባት ።

አስቴር እኔ እኮ ትናንት እንደዚያ ሲሳደቡ ሁላችንም ታፍሰን የሔድን መስሎኝ ነበር ።

ከበደች አሁንስ ይቀርልን ብለሽ ?

አስቴር ምን ያደርጉናል ።

ከበደች ምን ዐውቄ እንግዲህ ።
(አልማዝ ጀበናውን ይዛ ትወጣለች ።)

አስቴር ትናንት የስካር ቀን ነበር ።

ከበደች ያንቺው ሰውዬም ሰክሮ ነበር?

አስቴር ድብን ብሎ ።

ከበደች ታዲያ እሱ እንደዚያ ጅል አይቀባጥር ።

አስቴር እሱ ሲሰክር አይናገር ። እንዲያውም ይደብተዋል ።

ከበደች እሱ ይሻላል ።



(አልማዝ በችኮላ ባዶ እጅዋን ትመጣለች ።)

አልማዝ (እጅዋን በፍርሃት እያርገበገበች) እትይዬ! እትይዬ! ጉድ ፈላብን ።

ከበደች ምንድን ነው ነገሩ ?

አልማዝ ሁለት ሰዎች ከበር ቁመው ወደ ፖሊስ ጣቢያ ትፈለጋላችሁ ይላሉ ።

ከበደች ፖሊሶች ናቸው ?

አልማዝ ኧረ አይደሉም ።

ከበደች ታዲያ ምንድን ናቸው?

አልማዝ ምን ዐውቄ ! (አንድ የሲቪል ልብስ የለበሰ ፖሊስ ወደ በሩ ይመጣል ።)

ፖሊስ አትወጡም እንዴ ?

ከበደች (በድንጋጤ) ኧረ እንመጣለን ።

ፖሊስ ታዲያ ቶሎ ተነሡአ !

ከበደች እሺ ፤ ልልበስና መጣን ።

ፖሊስ ቶሎ በሉ !

ከበደች (ከፍርሃት ጋር) እሺ ! ዕቃውን ቶሎ አንሡና ነጠላ ልበሱ ።
(ፖሊሱ ሲመለስ አልማዝ አስቴርና ፀሐይ ሲወጡ ከበደች ፒጃማዋን አውልቃ ቀሚሷንና ነጠላዋን ትለብሳለች። ወደ ቁም ሳጥኑ መስታወት ቀረብ ብላ መልኳን ለማስማመር ትሞክርና በፍርሃት ተቻኩላ ወደ በሩ ስትራመድ መጋረጃው ይዘጋል ።)

# ትርእይት ፪

ከጥቂት ቀኖች በኋላ፤ጊዜው ከጥዋቱ ፫ ሰዓት ተኩል ቦታው አዲስ አበባ ውስጥ የአንድ ልዩ ፍርድ ቤት ዝግ ችሎት ክፍል ። ሦስት ዳኞች ተሠይመዋል ። ከበደች አልማዝ አስቴር ፀሐይ በክፍሉ ውስጥ በአንድ አግዳሚ ወንበር ላይ ተቀምጠዋል ። ፍርሃትና ድንጋጤ ይታይባቸዋል ። ፖሊሱ በሕግ አስከ ባሪነት ከዳኞች ፊት ለፊት ተቀምጧል ። ተዘራ ሁለት እጆቹ እንደ ታሠሩ ከዳኞች ፊት ቁሟል ። ጠመንጃ የያዘ አንድ ፖሊስ ከኋላው በተጠንቀቅ ቁሟል ። ከሰብሳቢው ዳኛ ፊት ትልቅ ፋይል ተቀምጧል ። ሰብሳቢው ዳኛ መነጽሩን ካፍንጫው ጫፍ ድረስ አውርዶታል ። ተዘራን በቍጣ ይመለከተዋል ። መጋረጃው ሲከፈት ወሬው እንደቀጠለ ነው ።)

**ሰብሳቢ ዳኛ** — እኮ ! አትድረቅ ! ተናገር ፤ ገጀልጃላ ጅል ንፍጣም ! ለመሆኑ ንጉሠ ነገሥቴ የሚሰደቡ ባንተ አፍ ነው ?

**ተዘራ** — አልወጣኝም ክቡር ጌታዬ !

**ሰ. ዳኛ** — ዓይንህ ይውጣ!

**ተዘራ** — (እጅ እየነሣ) እሺ!

**ሰ. ዳኛ** — ዝርፍጥፍጥ ዘርፈጥፋጣ! ዝርግፍግፍ ዘርገፍጋፋ! ዝርክርክ ዘረክራካ!

**ተዘራ** — ነኝ ።



**የቀኝ ዳኛ** — ጊዜው በስድብ አለቀ እኮ ! ፍሬ ነገሩን እን ጠይቀው እንጂ !

**ሰ. ዳኛ** — እንግዲህ እሺ ካለህ ጠይቀዋ !

**የቀኝ ዳኛ** — ወንድም ነገሩ ተጣርቷል ። አሁን ማስቸገሩ ምን ያደርግልዎታል ?

**ተዘራ** — ምኑ ክቡር ጌታዬ?

**የግራ ዳኛ** — ተዘራጣጭ መሆንህ ።

**ተዘራ** — (በፍርሃት ዓይኑን ወደ ዓቃቤ—ሕጉና ወደ ሰብሳቢው ዳኛ እያጉረጠረጠ) ማንን ዘረ ጠጥሁ ?

**ሰብ. ዳኛ** — ዝምበል ! ሌባ !

**ተዘራ** — (እጅ እየነሣ) እሺ ፣ ሌባ ነኝ !

**የቀኝ ዳኛ** — (እየሳቀ) እንዴ ! በሌብነቱም እኮ ! መቀጣት አለ !

**ተዘራ** — ልከራከር እንዴ ጌታዬ ? እንደትራፊኩ ደንብ መስሎኝ እኮ ነው ! ‘አጥፍተሃል ? አላጠፋህም ?’ ሲባሉ አጥፍቻለሁ ማለት ከጭቅጭቅ ስለሚያድንና ቅጣቱን ስለሚያቀል....

**ሰብሳቢ ዳኛ** — በቃህ አቧሬ አፍ! የራስህን ጉዳይ ተናገር !

**ተዘራ** — እናገራለሁ ።

**ሰ. ዳኛ** — አጥፍተሃል ? አላጠፋህም ?

**ተዘራ** — አልተሳደብሁም ።

**ሰ. ዳኛ** — (ወደ ፋይሉ እየተመለከተ) ይኸው በምርመራው መዝገብ ላይ የሰፈረውና ራስህ አምነህ የፈረምኸበት ቃልህ እያስረዳ !

ተዘራ — አዬ ጌታዬ ! ሥቃዬን የት አዩት ?

ሰ. ዳኛ — ምን ማለትህ ነው ?

ተዘራ — በሥቃይ ብዛት አመንሁ !

ሰ. ዳኛ — ማነው ያሠቃየህ ?

ተዘራ — (ወደ ሕግ አስከባሪው በታሠሩ እጆቹ እያመለከተ) አንዱም እሱ !

ዓቃቤ ሕግ — ኧረ ይህ ዋሾ !

ተዘራ — (እግሩን እያነሣ) የግሬ ውስጥ ይታይ!

ዓቃቤ ሕግ — (እየተነሣ) ታዲያ ሞያሌ የበላህን ሁሉ በፖሊስ ልታመካኝ ነው ?

ተዘራ — ሐሰት ! እግሬን ከተወለድሁ አፈር ነክቶት የማያውቅ አዲስ አበባ ተወልጄ ያደግሁ የታላቅ መኳንንት ልጅ ነኝ ።

ዓቃቤ ሕግ — ታዲያ ማን ነካህ ?

ተዘራ — መንካት ? አነከትኸኝ እንጂ !

ሰ. ዳኛ — በል እሺ ! አንተ ተገድጄ ነው አልህ አይደለም ?

ተዘራ — አዎን ።

ሰ. ዳኛ — እሺ ፤ ቆየኝ ! ሕግ አስከባሪ ምስክሮችህን አቅርብ ።

ዓቃቤ ሕግ — ወይዘሮ ከበደች ! (ከበደች በድንጋጤ ተነሣና ወደ ዳኞች ፊት ትቀርባለች ።)



ሰ. ዳኛ — (በጠረጴዛው አንድ ወገን ላይ ያለውን መጽሐፍ ቅዱስ ወደ ፊቷ አቅርቦ) ስም ከነ አባት ?

ከበደች — ከበደች ተሠራ ።

ሰ. ዳኛ — የሱ ልጅ ነዎት እንዴ ?

ከበደች — የማን ?

ሰ. ዳኛ — የተከሣሹ ተዘራ ?

ከበደች — ተዘራ አይደለም አባቴ ። ተሠራ ነው ።

ሰ. ዳኛ — ይህ ወሽካታስ ምንሽ ...ኧ... ይቅርታ ምንዎ ነው?

ከበደች — ወዳጄ ።

ሰ. ዳኛ — የት ተገናኛችሁ ?

ከበደች — ከመጠጥ ቤቴ ።

ሰ. ዳኛ — መጠጥ ቤት አለዎት እንዴ ?

ዓቃቤ ሕግ — ከሱዋ ቤት ሰክሮ አይደለም እንዴ የቃዠው።

ተዘራ — ታዲያ ቅዠት ከሆነ ለምን ንቃችሁ አልተዋችሁኝም ? ደሞ ቅዠት ! ግን ምን ይሁን! አንተ ሰላይ፤አንተ አሣሪ ፤ አንተ ገራፊ አንተ መስካሪና አንተ አቃቤ-ሕግ በቃ ! ሕግ ይኸ ነው !

ዓቃቤ ሕግ — (ለዳኞች) ዕዩ ጌቶቼ! ድፍረቱን ።

ተዘራ — ኧረ እኔ የወጣልኝ ፈሪ ነኝ ።

የግራ ዳኛ — በንትርክ ጊዜው አለፈኮ!

ሰ. ዳኛ — (ለተዘራ) በቃህ አትለፍልፍ ! (ወደ ከበደች እየተመለከተ) እሺ የኔ እመቤት! መጠጥ ቤት አለኝ አሉ ?

ከበደች — አዎን አለኝ ።

ሰ. ዳኛ — በየት አካባቢ ? (የግራና የቀኝ ዳኞች ፈገግ ይላሉ ።)

ከበደች — ካዛንችስ ።

ሰ. ዳኛ — ካዛንችስ እምኑ ጋ ?

ከበደች — እርሻ ሚኒስቴር ጥግ ።

ሰ. ዳኛ — ገባ ብሎ ነው ? እመንገድ ዳር ?

ከበደች — ጥቂት ገባ ይላል ።

ሰ. ዳኛ — እሺ ይሁን ፤ ዕድሜዎ ስንት ነው ?

ከበደች — ቍጥሩን አላውቀውም ። ግን እናቴ ፈረንጁ በገባ በዓመቱ ነው የተወለድሽ ብላኛለች ።

ሰ. ዳኛ — በጣሊያን ጊዜ ?

ከበደች — አዎን ።

ሰ. ዳኛ — ደኅና ሒደዋልና! እሺ ። ከተከሳሹ ጋር.... እ ! ሃይማኖትዎ ?

ከበደች — አማራ ።

ሰ. ዳኛ — ዘርዎን ማለቴ አይደለም ፤ ሃይማኖትዎ?

ከበደች — ዘሬም ሃይማኖቴም አማራ ነው ።

የቀኝ ዳኛ — (ፈገግ ብሎ) ኦርቶዶክስ መሆናቸው ነው ።



ከበደች — እኔ ንጡህ ክርስቲያን ነኝ ።

የቀኝ ዳኛ — ለመሆኑ ቤተ ክርስቲያን የሚስሙት የት ነው ?

ከበደች — (ኮስተር ብላ) እንዴ! ውራዬል! ገብሬል ፥ ሥላሴ ባታ ነዋ! ዓመት ባል ሲሆንም ንጡህ ከሆንሁ ብዙ ደብር እስማለሁ ። ቁልቢም በየዓመቱ ቀርቼ አላውቅም ። ደሞ ሌላ ገር ደስ ገንደስ አመጡብኝ ? (ሦስቱም ዳኞች ይስቃሉ ።)

ከበደች — እኔ እውነቴን ነው ። ሴተኛ አዳሪ ብሆን ሃይማኖቴን የካድሁ መሰላችሁ! እናት አባቴ እኮ ! ላሊበላን አኩስም ጢዎንን የሳሙ ናቸው ።

የቀኝ ዳኛ — ያው ኦርቶዶክስ መሆንዎ ነው ።

ከበደች — ኧረ እኔ አይደለሁም ።

የቀኝ ዳኛ — ታዲያ ምንድን ነዎት ?

ከበደች — ምነው ጌታዬ ? አማራ ነኝ አልሁ እኮ !

ሰ. ዳኛ — እሺ ፤ እንግዲህ ይሁና ! (መጽሐፍ ቅዱሱን እያመለከተ) እጅዎን እዚህ ላይ ይጫኑ ። (ከበደች እጅዋን በመጽሐፍ ቅዱሱ ላይ ትጭናለች ።) ይማሉ ።

ከበደች — ምን አደረግሁ ።

ሰ. ዳኛ — ምንም አላደረጉ ፤ ለምስክርነት ነው ።

ከበደች — እሺ ምያለሁ ። (ዳኞች ይስቃሉ ።)

ሰ. ዳኛ እሺ ይሁን ፤ እንግዲህ ምለዋል ፤ እውነት መናገር አለብዎት ።

ከበደች ኧረ እኔ ምን አስዋሸኝ ?

ተዘራ ኧረ! እሷ ባይሆን በሒሳብ ላይ እንጂ በሌላ መች ትዋሻለች ።

ሰ. ዳኛ ቀዳዳ ! ዝም በል !

ተዘራ (እጅ እየነሣ) እንዳሉ ።

ሰ. ዳኛ ታዲያ ይህ ጣፋርዲ ጥፉርፉድ ጌታዬን ሲሳደብ አልሰሙም ?

ከበደች ማንን ?

ሰ. ዳኛ ጃንሆይን ።

ከበደች ሰምቻለሁ ።

ተዘራ አልሰማችም ። ያመነቺው እንደኔ አንኮላሽተዋት ነው ።

ሰ. ዳኛ ቀዳዳ ! ሴት ይንኮላሻል ?

ዓቃቤ ሕግ እሱንስ ማን ነካው ?

ተዘራ ራስህ! ወሀ የሞላበት ፊያሽኮ አላንጠለጠልህብኝም ?

ዓቃቤ ሕግ ኧረ ምን ዓይነቱ ዋሾ ነው !

ተዘራ የግሬ ውስጥም ይታይ ።

ዓቃቤ ሕግ ምን እግሬ እግሬ ! ይላል !

ሰ. ዳኛ ዝም አትለውም! ተመስክሮበታል ። ይልቅ ሌሎችን ምስክሮች ጥራ ።



ዓቃቤ ሕግ ወይዘሮ አስቴር !

አስቴር (እየተነሣች) አቤት !

ዓቃቤ ሕግ ወደዚህ ቀረብ በይ ! (ትቀርባለች ።)

ሰ. ዳኛ ነይ መጽሐፉን ያዥ ። (አስቴር ቀረብ ብላ መጽሐፍ ቅዱሱን ታነሣለች) እንዴ ! አስቀምጪው እንጂ ፤ የት ትወስጂው! (በድንጋጤ ታስቀምጠዋለች) በይ እጅሽን ጫኚበት ። (እጅዋን በመጽሐፍ ቅዱሱ ላይ ትጭናለች ።) በይ ማይ ።

አስቴር ምን ብዬ ?

ሰ. ዳኛ የሰማሁትን አልደብቅም ብለሽ ።

አስቴር አልደብቅም ምያለሁ ።

ሰ. ዳኛ (ፈገግ ብሎ) እሺ ፤ ይህ ቀዳዳ ጃንሆይን ሲሰድብ አልሰማሽም ?

አስቴር (በፍርሃት) ሰም. ቻ. ለሁ ።

ተዘራ አቤት ውሸት! አቤት ያንት ያለህ! ያን ጊዜ ስሳደብ ነበራችሁ ?

አስቴር አዎን ።

ተዘራ አንቺ ቀጣፊ ፤ እኔ ስሳደብ ቢራ ይዘሽ ወደ ጓዳ አልሔድሽም ነበር ።

አስቴር እንዴ ! ሰምቻለሁ ።

ተዘራ በጆሮሽ እንኳ አልሰማሽም ።

ሰ. ዳኛ ግን መሳደብህን አንተም ታውቀዋለህ?

ተዘራ — የለም ረስቼ ነው ፤ አልተሳደብኹም ።

ሰ. ዳኛ — በቃ ! አሁንማ በሙሉ ተረጋገጠብህ ።

ተዘራ — ተረጋገጥህ ? አዎ ! ዐውቀውልኛል ።

ሰ. ዳኛ — ሕግ አስከባሪ ! ይህ ሰው አሁንም ያሾፋልና! ለአንድ ሳምንት በምርመራ አቆይተህ ብታ መጣው ይሻላል ።

ተዘራ — (ዕብድ ለመምሰል በመሞከር) እ! ኳስ ! (በታሠሩ እጆቹ ልብሱን ለመቅደድ ይሞ ክራል ። ሁሉም ግራ ይገባቸዋል ።) በርታ! በርታ 8 ቁጥር በርታ! በርታ! አንሸነፍም! (ኳስ እንደሚመታ እግሩን ወደላይ ያጐናል ።) ገባች! ጐል! እኔ ነኝ ያገባኋት! እ! እ! እ! (በጀርባው ይወድቅና ይንፈራፈራል ።) ግር !ር ! ር! ር! ር! ቢር ! ር. ር! ር! እኽ ! ኽ ! ኽ! ኽ! በኳስ አንሸነፍም ። (በቅልጥ ፍና ተነሥቶ የዳኞችን ጠረጴዛ በርግጫ ይመታዋል ። በጠረጴዛው ላይ ያሉት ፋይ ሎችና መጽሐፍ ቅዱሱ በየአቅጣጫው ይወ ድቃሉ ። ዳኞችና አቃቤ ሕጉ በድንጋጤ ይነሡና ለመሸሽ ይቃጣሉ ።)

ሲ. ዳኛ — ፖሊስ ! ምን ትሠራለህ ?

ፖሊስ — ምን ላድርግ ?

ሰ. ዳኛ — በወህኒ ቤት የዕብዶች ክፍል አለ አይደ ለም ?

ፖሊስ — አለ !



ሰ. ዳኛ — ውሰድ ።

ፖሊስ — (ወደ ሁሉም ዳኞችና ዓቃቤ ሕግ እየተመ ለከተ) ልውሰድ ?

ሦስቱ ዳኞች — ውሰደው! ውሰደው! ውሰደው!

ዓቃቤ ሕግ — እኔ ብወስደው ይሻል ነበር ።

ተዘራ — (አሁንም ዕብድ በመምሰልና በመፍራት) ኖ ! ኖ! ምርመራና በኳስ መሸነፍ ክፉ ! እ! እ! እ! ወህኒ ቤት ክፉ! ወህኒ ቤት መግባት እፈልጋለሁ ! ጠቅልን ሰድቤም ቢሆን ኳስ ስንሸነፍ ከማይ ወህኒ ቤት መግባት እፈል ጋለሁ ። እ! እ! ኳስ ! ምርመራ ! ክፉ !

ሰ. ዳኛ — ወህኒ ቤት ይሒድ አቃቤ ሕግ!

ዓቃቤ ሕግ — እሺ ይሁን ።

ሦስቱ ዳኞች — አዎ ፤ ይሒድ !

ሰ. ዳኛ — አዎ! ግን ወደ ዕብዶች ክፍል ።

ተዘራ — (ደስ ያለው ዕብድ መስሎ) አ! ወደ ወንድ ሞቼ ልሔድ ነው ! ዕል ! ል !ል ! ል! (እየደጋገመ ይዘላል ። በታሠሩ እጆቹ ለማ ጨብጨብና ለመጨፈር ይሞክራል ።)

ዳኞች — ውሰድ ! (ተዘራ በጭፈራ መልክ እየዘለለ ፖሊሱ እንደያዘ ይወጣል ፤ ዳኞችና አቃቤ ሕጉ ይቀመጣሉ ። )

ሰ. ዳኛ — (ለነከበደች) ወይ ግሩም ! ምን ዓይነት ጉድ ነው እባካችሁ? ለመሆኑ ዕብደት

ሞክሮት ያውቃል ወይስ እኛን ለማወና በድ ነው?

ከበደች — ከጠርሙስ ውስኪ በኋላ ሞክር ያደርገዋል ።

የቀኝ ዳኛ — ያብዳል ማለት ነው?

ከበደች — ማበድ ሳይሆን ወፈፍ ማድረግ ነው ።

የቀ. ዳኛ — እሱስ በሁሉም የተለመደ ነው ።

ሰ. ዳኛ — ዓቃቤ—ሕግ! እሺ ሌለኛውን አስገባ ።

(ዓቃቤ—ሕጉ ይወጣል ።)

የቀኝ ዳኛ — እንግዲህ ሴቶቹ ይሒዱ!

ሰ. ዳኛ — አዎ ፤ ይሒዱ ። የኔ እኅት! ስንፈልጋችሁ ትመጣላችሁ ። ወይም ጉራ ብለን እንጠይቃችኋለን ። (ሴቶቹ ይወጣሉ ። ዓቃቤ—ሕጉ በሁለት ፖሊሶች የሚታጀበውን ፈረደን አስከትሎ ይገባል ። ፈረደም ሁለት እጁ በሰንሰለት ታሥሯል ። ወደ ዳኞች ፊት ቀረብ ብሎ ይቆማል ። ዳኞች የወደቁትን ፋይሎችና መጽሐፍ ቅዱሱን እያነሡ በጠረጴዛው ላይ ያስቀምጣሉ ።)

ሰ. ዳኛ — ዛሬስ አላመጣህም ?

ፈረደ — ምኑን ጌታዬ ?

ሰ. ዳኛ — የምሕረት መለመኛውን ማመልከቻ ።

ፈረደ — ምን አጥፍቼ ነው ምሕረት የምጠይቅ?



ሰ. ዳኛ — ከዚህ ይበልጥማ ክርስቶስን እንደገና ልትሰቅለው ኑሯል ?

ፈረደ — ይህን ጉዳይ ከክርስቶስ ጋር ምን አገናኘው ?

ሰ. ዳኛ — የጌታዬን ፤ ከፖስታ አቀባይነት አውጥቶ የፈጠረኝን አምላኬን መንግሥት ለመገልበጥ በተጠነሰሰ ሤራ መግባት ጥፋት አይደለም?

የቀ. ዳኛ — ይተዉ እንጂ ብላታ! ፈጣሪማ አይበሏቸው ።

ሰ. ዳኛ — ወይድ እባክህ! ታዲያ ማን ፈጠረኝ እግዜርን እንደሆነ አላየሁት!

የቀ. ዳኛ — አይ! ይኸን አባባል እሳቸውም ቢሆኑ የሚወዱት አይመስለኝም ።

ሰ. ዳኛ — እሱን ተወው! ቢሰሙ እንዴት ልባቸውን ባረካው! (ሁሉም ይስቃሉ ።)

ፈረደ — ታዲያ እንዲህ ያለ አስተዳደርን መቃወም ወንጀል ነው?

ሰ. ዳኛ — ምንስ ቢሆን ባገር ጉዳይ አንተን ምን አገባህ?

ፈረደ — ኢትዮጵያ የናንተ አገር ብቻ ናት ማለት ነው ?

ሰ. ዳኛ — ብትኖርባት ብቻ መች አነሰህ ? ደግሞስ ምን ጐደለህ ? ሹመቱንም ቢሆን ራስህ ነህ አሻፈረኝ ብለህ የተውኸው ።

ፈረደ — ሰውን ፈጣሪዬ ማለት ስለማልችበት ነው።

ሰ. ዳኛ — (በቍጣ) በል ስደበኛ!

ፈረደ — ኧረ እኔ አልሳደብም ።

ሰ. ዳኛ — ክፍት አፍ! አሳይኻለሁ ።

ፈረደ — ዐይቼልዎታለሁ እኮ ! ዕድሜ ልክ እሥራት አከናንበውኝ የለ ! ረሱት እንዴ?

ሰ. ዳኛ — ልሰቅልህም እችል ነበር እኮ!

ፈረደ — አሁንም ይችላሉ! ይህ ቢሆንማ ነው በፍርድ! ያሠሩትን ሰው በየቀኑ እየጠሩ የሚያሠቃዩት!

ሰ. ዳኛ — እኔማ ምሕረት ለምነህ እንድትፈታ ብዬ ነበራ !

ፈረደ — ይህን ዐውቀዋለሁ ፤ አልፈታም ።

ሰ. ዳኛ — ምሕረት ከለመንህ ለምን አትፈታም? አብረውህ ከታሠሩት ወንበዴዎች ጓደኞችህ አንዳንዶቹ ተፈተዋል ። ሌሎችም እሥራቱ ወደ ግዞት ተለውጦላቸዋል ።

ፈረደ — አዎ! አልፎ አልፎ ለጥቅሙ እምነቱን የሚሸጥ አይጠፋም ።

ሰ. ዳኛ — አሁንም ምሕረት ለምን ።

ፈረደ — ምን ብዬ?

ሰ. ዳኛ — እኔ ምስኪን ኃጢአተኛ ፤ ወንጀለኛና ዐመፀኛ ከሐዲ ነኝ ፤ ንጉሥ እንደ እግዚአብሔር መሐሪ ፤ የዜጎቹ ሁሉ ፈጣሪ ፤ ሩኅሩኅ ወር



ቃዊ ቃላት ተናጋሪ ነውና! ለፈጸምሁት በደል ሁሉአፈር እየቃምሁ ምሕረት እለምናለሁ ፤ በል ።

ፈረደ — (እየሳቀ) አልልም ።

ሰ. ዳኛ — ይህ ጋግርትህ ቢለቅህና ምሕረት ለምነህ ብትፈታ ይሻልኻል ።

ፈረደ — እርግጥ ነው ፤ ብፈታ ይሻለኛል ፤ ግን አጥፊ ነኝ አልልም ።

ሰ. ዳኛ — እኮ! ለምን ?

ፈረደ — አላጠፋሁም ።

ሰ. ዳኛ — (በቍጣና በጩኸት) የጃንሆይ መንግሥት ፣ ጨቋኝ ፈሪ ነው ፤ በኋላም ይወድቃል አላልኽም ?

ፈረደ — አላልኹም ።

ሰ. ዳኛ — አልኸ እንጂ ። ዓይን ለዓይን ልትክድ ነው?

ፈረደ — እኔ እንኳ የተናገርሁት ስለጠቅላላው ነበር። ግን ይህንም ካሉ ስለ ጃንሆይ መንግሥት ፍጻሜስ ማን ያውቃል ?

ሰ. ዳኛ — እኛስ ባሮቻቸው ?

ፈረደ — ስለ ራስዎ ፍጻሜስ ማን ያውቃል ?

ሰ. ዳኛ — ኧረ ወይድ! ሳለ ጠቅል ምን እንዳይመጣ?

ፈረደ — ሰው ናቸውና ምናልባት ያልኖሩ እንደ ሆነስ ?

ሰ. ዳኛ — ሰው ?

ፈረደ — ታዲያስ? ሰው አይደሉም እንዴ?

ሰ. ዳኛ ጌታዬ ከሰው ሁሉ በላይ ነው ።

ፈረደ እሺ እንዳሉ ይሁንልዎት ።

ሰ. ዳኛ አሁንም ምሕረት ለምን ።

ፈረደ አልለምንም ።

ሰ. ዳኛ ከተፀፀትህ አሁንም ምሕረት እናደርግል ኻለንኮ!

ፈረደ እንኳን ለኔ ፤ በደለን ለምትሉት አንድ ሰው ቀርቶ ምንም ላልበደላችሁና ለሚያመልካችሁ ሕዝብ ምሕረት አታውቁም ።

ሰ. ዳኛ ችኮ! አሁንም እሥራት አልሰለቸህም ?

ፈረደ ዘጠኝ ዓመቴ አይደል? ለምን አያንገፈግፈኝም ?

ሰ. ዳኛ ታዲያ ለምን ምሕረት አትለምንም ?

ፈረደ እግዚአብሔርን እየለመንሁ ነው ።

ሰ. ዳኛ ጃንሆይንስ? መናቅህ ነው ?

ፈረደ አልናቅሁም ።

ሰ. ዳኛ ተው ለምን ፤ ይሻልኻል !

ፈረደ ምን ፍጡር ነው የሚሉኝ ?

ሰ. ዳኛ እኮ! ጥፋትህን አምነህ ምሕረት መለመን አለብህ ።

ፈረደ አላጠፋሁም ነው እኮ የምለው ። (በጣም ቈጣ ብሎ) ሕግ እናውቃለን ትላላችሁ ።



ለምን እሥረኛ እየጠራችሁ ታጉላላላችሁ?

ሰ. ዳኛ እኛማ ልናስፈታህ ብለን ነበራ !

ፈረደ አይመስለኝም ፤ እኔን አስቀባጥሮ ባመነው ወንጀሉ ጠፋ ለማሰኘት ነው ።

ሰ. ዳኛ እምቢ ማለትህ ነው ?

ፈረደ (በመሰልቸት) አዎ እምቢ አልሁ ።

ሰ. ዳኛ (ለዘቦች) በቃ ወስዳችሁ በጥብቅ እሠሩ !

ፈረደ ግድ የለም ፤ እግዜር ባለበት ቀን እፈታለሁ።

ሰ. ዳኛ እናያለን

ፈረደ ታያላችሁ ።
(ከዘቦች ጋር ሲወጣ መጋረጃ ይዘጋል ። )

# ትርኢት ፫

ጊዜው ከሌሊቱ ስምንት ሰዓት ነው ። ቦታው ዓለም በቃኝ ወህኒ ቤት ውስጥ የሚገኝ የዕብዶች ክፍል ። ክፍሉ በረት የመሰለ ነው ። ዕብዶች በየቦታው ፈንጠር ፈንጠር ብለው ተቀምጠው የየራሳቸውን ጉዳይ ይዘዋል ። አንዱ ቤት ለመሥራት እንደሚያዘጋጅ መሬቱን በባዶ እጁ ይለ ካል ፤ ሌላው ይዘፍናል ።

፩ኛ ዕብድ (መጽሐፍ የሚተረጕም በመምሰል) አንድም መልካም ሰዎች እነማን ናቸው ቢሉ ሰውን የሚያፈቅሩ እግዚአብሔርን የሚ ፈሩ ፤ ተግተው የሚሠሩ እውነት የሚናገሩ ፤ ክፋትን የሚጣረሩ ፤ አንድም ክፉ ሰዎች እነማን ናቸው ቢሉ ሳይሠሩ የሚበሉ ሰውን የሚያጉላሉ ፤ አንድም ሳይዘሩ የሚ ያጭዱ ሳይገዙ የሚነዱ በማጭበርበር የሚነግዱ ሳያገቡ የሚ . . አ ! አ! ይኸንስ በሥራ እንጂ በቃል የሚወደው የለም ። ይቅር ። (ይነሣና ምራቁን በጁ ላይ እንትፍ እንትፍ ብሎ ፊቱን ያባብሳል ። ሁለተኛው ዕብድ ቤት ለመሥራት ሲሞክር ከነበረበት ይነሣል ።

፪ኛ ዕብድ ከዓለም አንደኛ አይደለም ጌታዬ ?

፩ኛ ዕብድ ምኑ ?

፪ኛ ዕብድ ይህ ቤተ መንግሥት ።



፩ኛ ዕብድ ግሩም ድንቅ!

(፫ኛና ፬ኛ ዕብድ) በመጨቃጨቅ ላይ ናቸው ።)

፫ኛ ዕብድ አንተ ቆይ ግዴለም ብቻ ከዚች ልውጣና እንተያያለን ።

፬ኛ ዕብድ ምን ታደርገኛለህ ?

፫ኛ ዕብድ (ጡጫውን እያሳየ) እነፋኻለሁ ።

፬ኛ ዕብድ በምን?

፫ኛ ዕብድ በቦክስ ።

፬ኛ ዕብድ ታዲያ አሁንስ አለሁልህ አይደለም ?

፫ኛ ዕብድ አሁን እጄ አይመታማ !

፬ኛ ዕብድ ለምን!

፫ኛ ዕብድ ዐብዱል ፤ አታየውም ከኛ ጋር ታሥሮ ?

፬ኛ ዕብድ (እየሳቀ) እውነትህን እኮ ! ነው ።
አሁን እኛ በበደልን እጃችንና እግራችን አብሮ መታሠሩ ምን ይባላል ?
በል አሁን እጆችህን ልቁረጥልህና ወደ አራዳቸው ተመልሰው ይዘንጡ ። (ይነሣል ።)

፫ኛ ዕብድ ተው ቁጭ በል! እጄ የሠራውን ወንጀል ብታውቅ እሱን እዚህ ትተህ እኔን ታስወ ጣኝ ነበር ።

፬ኛ ዕብድ እጅህ ምን ሠርቷል ?

፫ኛ ዕብድ እሱስ ምንም አይደል ።

፬ኛ ዕብድ እኮ ምንድን ነው?

፫ኛ ዕብድ — እህ ! ይኸ ምን አለው ብለህ ነው? አንድ ቀን መርካቶ ላይ አንዲት ሴትዮ አባሮ በድንጋይ ገድሏል ።

፬ኛ ዕብድ — ምን ዓይነቱ ጅል ነው እባካችሁ! ይኸ ነው ቁም ነገሩ ? ለዚህማ የኔ እጅስ በሽ ጉጥ ሁለት የሥራ አለቆቼን ገድሎ የለ! እኔ እኮ ቁምነገር ሊነግረኝ ነው ብዬ !

፭ኛ ዕብድ — (እየተንጐራደደ) እንዴት ሳይፈሩን በፊታችን ወንጀላቸውን ይናገራሉ? ዘበኛ አሁን ሁሉንም ከያለበት ጥራ !

(ወደ ፬ኛ ዕብድ እየተመለከተ) አንተ ወስላታ እኔ አለቃህ መሆኔን አታውቅም?

፬ኛ ዕብድ — ዐውቃለሁ ።

፭ኛ ዕብድ — ታዲያ ለምን ገደልኸኝ ?

፬ኛ ዕብድ — በማበድ ተሳስቼ ነው ጌታዬ ።

፭ኛ ዕብድ — በል አብጃለሁ ብለህ ማል ።

፬ኛ ዕብድ — እሺ እምላለሁ ። ግን ምን ብዬ ልማል ?

፭ኛ ዕብድ — ዋሾ እንደ . . . . ፤ አድርባይ እንደ ዝግ ችሎት ዳኛ እንደ ሀብታም ስስታም እንደ ቆማጣ ፎኮታም ያድርገኝ በል ።

፬ኛ ዕብድ — አሜን ሁላችንንም ከዚህ ቤት አውጥቶ ዳኞችና ፖለቲከኞች ያድርገን ።

፭ኛ ዕብድ — ይኸን ከፈለግህ እኔን ንጉሥህን ደጅ አትጠናም ? በል አሁንም የአዶልፍ ሂትለር አለቃ አድርጌ ሹሜሻለሁ ። (፬ኛ ዕብድ እጅ ይነሣል ።)



፭ኛ ዕብድ — በ፬ኛው ዕብድ ጀርባ ላይ እንደ ወንበር ይቀመጥበታል ።

(ወደ ሦስተኛው ዕብድ እያመለከተ) አንተም ሴት ገድለኻል ።

፫ኛ ዕብድ — አዎን ክቡር ጌታዬ ።

፭ኛ ዕብድ — በምን ገደልኻት ?

፫ኛ ዕብድ — በፍቅር ።

፭ኛ ዕብድ — በርግጥ ትወዳት ነበር ?

፫ኛ ዕብድ — ነፍሴ እስከምትጠፋ !

፭ኛ ዕብድ — አሁንም ፈልገህ አላገኘኻትም?

፫ኛ ዕብድ — ምኗን ?

፭ኛ ዕብድ — የጠፋቺውን ነፍስህን ።

፫ኛ ዕብድ — በመፈለግ ላይ ነኝ ። እሷን ልፈልግ ስሮጥ ነው ይዘው እዚህ ያመጡኝ ።

፭ኛ ዕብድ — በል አላገኘኋትም ብለህ ማል ።

፫ኛ ዕብድ — እሺ ምን ብዬ ልማል?

፭ኛ ዕብድ — ስግብግብ ዋጋ አስበልጦ እንደሚሸጥ ነጋዴ፤ ሕግን እንደማይከተል ሰው ወንበዴ ስሙን እየለወጠ እንደሚጽፍ ሰው ለከስካሳ ፤ በሐሳቡ እንደማይረጋ ሰው ለፈስፋሳ ፤ ወባ እንዳደቀቀው ሰው ኮሳሳ ፤ እንደ ዕብድ ሰላም የሚነሣ ያድርገኝ በል ።

፫ኛ ዕብድ — እሺ ያድርገኝ ።

፭ኛ ዕብድ — በሉ አሁን የአምስት አምስት ቀን ከባድ

ዝላይ በይኼባችኋለሁ ። (ሁለቱ ዕብዶች ዝላይ ሲቀጥሉ ሌሎችም አብረው ይዘ ላሉ ።)

፩ኛ ዕብድ (ለሌሎች ዕብዶች) ተዉ! ተዉ! ለእናንተ ይኸ ክብር አይፈቀድም ።

፫ኛ ዕብድ ጉድ ነው የሚያስብ አእምሮ እያለኝ ዕብድ አሉኝ!

፩ኛ ዕብድ (በቁም ነገር መልክ) ተው በሳይንስ አታ ፊዝ ፤ የሚያስብ ጨጓራ እንጂ አእምሮ አይ ደለም ።

፫ኛ ዕብድ (ሳያዳምጥ ንባቡን ይቀጥላል ።)
እሥራት መሪር ነው በብዙ መንገድ ፤
ፍላጎት አይታይ ሁልጊዜ የግድ ።
ከፋኝ ቢሉ ይብስ መባል አዋኪ ዕብድ ።

፩ኛ ዕብድ (ጣልቃ በመግባት) አንተ ስንናገርህ እን ዴት አትሰማም ? ንጉሥህ አይደለንም ? አልታዘዝም ማለትህ ነው ?

፫ኛ ዕብድ (እንደ ወንበር ፩ኛው ዕብድ ከተቀመጠ በት) ኧረ ከበዱኝ ጌታዬ !

፩ኛ ዕብድ ዝም በል ! እኛ በተሸከምንህ ደሞ ደከመኝ ! እኛ አንቀመጥብህ እንዴ ?

፫ኛ ዕብድ (ሶምሶን እንዳደረገው ቤቱን አፍርሶ ከጠ ላቶቹ ጋር አብሮ ለመሞት ከየግድግዳው ጋር እየታገለ ሕይወቱን ይሰናበታታል ።)



፫ኛ ዕብድ በቃ ደህና ሰንብች ሕይወት ቅሪ በቤቴ ።
ሐያቲ ሐያቲ ሕይወቴ ሕይወቴ !
እንዳልፈልግሽ አስጠላሽኝ !
እንዳልጨርስሽ አሳዘንሽኝ !
ሐያቲ ሐያቲ ፣ ሕይወቴ ሕይወቴ !
የኔ ነፃነቴ !

ሐያቲ ሐያቲ ሕይወቴ ሕይወቴ !
አልጨነቅም ካልኖርኩ ለሞቴ ።

መኖር አንድ ነው የለውም ሌላ ትርጉም ።
የሕይወት ጠላቶች ይበሉ ድርግም !
ሐያቲ ሐያቲ ሕይወቴ ሕይወቴ !
የኔ ነፃነቴ !
ውዷ ባለቤቴ ።
እንዲያ ሰወድሽ እጅግ በጣም ።
አለያየን ፍቅር አይጥም ።
አሁን ልጸፍ ወይ ? የፍቅር ግጥም ?
ጩኸ እስኪያነደኝ የውሀ ጥም ?
«ከኔ ጋር መኖሩ እንዲህ ካስከፋሽ !
በይ እኔም ሔድኹልሽ አገሩ ይስፋሽ! »
እንዳለው አንድ ሰውዬ እኔም ልተውሽና ።
አንቺም እንዳሻሽ በይ ቀና ቀና !
ሐያቲ ሐያቲ ሕይወቴ ሕይወቴ ፣
የኔ ነፃነቴ ።

ሴት አልፈልግም ግን ነይ በሞቴ ።
እኔ ሴት ስወድ አይቆርጥም አንጀቴ ።

፩ኛ ዕብድ (በፀጥታ ሲያዳምጥ ቆይቶ) ፍጹም ቅን አገልግሎትህን ከዚህ በይልጥ ማሳየት ስለ

| | |
|---|---|
| | ማትችል አሁን ላሳየሽው ፍጹም አገልግሎት የአሜሪካ ፕሬዚዴንትና የሩሲያ ጠቅላይ ሚኒስትር አድርገን ሹመንኻል ። (ገጣሚው ዕብድ ጫማ ይስማል ።) |
| ፯ኛ ዕብድ | የንጉሥን ጫማ ሊስትሮ ዐይቶት አያውቅም ፤ ለምን ? ቢሉ በሰው አፍ ነው እሚወለወለው ። (ከት ብሎ ይስቃል ። በመሐሉ ዘበኞች ተዘራን ይዘው ይመጣሉ ዕብዶቹ ግር ብለው ወደበሩ ይሔዳሉ ። ) |
| ፩ኛ ዘበኛ | (ለማስፈራራት) ተመለሱ ! በኮረንቲ እጠብሳችኋለሁ ! |
| ብዙ ዕብዶች | አይ !አይ ! አይ ! አይ ! ኮረንቲ ክፉ ! አልፈልግም ! (ወደ ኋላ ይሸሻሉ) እምቢዮ ! አንመጣ ! |
| ፪ኛ ዘበኛ | በቃ እጁን እንፍታና እናስገባው ። |
| ተዘራ | (በፍርሃት) ይጣሉኝ ይሆን ? |
| ፩ኛ ዘበኛ | እንዴ ! ጤነኛ ነህ እንዴ ? ታዲያ ለምን እስካሁን ስታስቸግር አሳደርኸን ? |
| ተዘራ | (እንደ ዕብዶች ለመሆን እየሞከረ) ኧ ! ጤና ክፉ ! (እየደጋገመ ይዘላል ። ) |
| ፪ኛ ዘበኛ | በቃ እጁን እንፍታና እናስገባው ። |
| ፩ኛ ዘበኛ | ግን እኮ ደኅና ነው ። |
| ተዘራ | (በጭንቀት እጅ እየነሣ) ደኅና ! እናንተስ ደኅና ? |



| | |
|---|---|
| ፩ኛ ዘበኛ | ደኅና ነው ፤ ግን እናስገባው ። |
| ተዘራ | አያያያያ ! |
| ፩ኛ ዘበኛ | (በችኮላ ) እንዴት ! |
| ተዘራ | ዕብደት ክፉ ! |
| ፪ኛ ዘበኛ | (ጠመንጃውን እያቀባበለ) በቃ! እጁን ፍታ! (ሁለተኛው ዘበኛ የተዘራን እጅ ይፈታል ። |
| ተዘራ | ዕል !ል ! ል ! (በበለጠ ጩኸት) ዕል ! ል! ል ! ል ! ል ! (ከፍርድ ቤት ሲወጣ እንዳደረገው እየዘለለ በዜማ ) በሕይወት ግባ በሕይወት ፤ ወንድማችን ለቅጣት ! |
| ፩ኛ ዘበኛ | ግባ ! (ወርውሮ ያስገባዋል ። ዕብዶች ግር ብለው ይከቡታል ። ) |
| ፩ኛ ዕብድ | (ቊጣ እንደጀመረ ውሻ ጥርሱን አግጥጦ ) እእእእእእ ! (አጐንብሶ ተዘራን ይቀርበዋል ።) |
| ተዘራ | ጓዴ እንዳትነክሰኝ ! እኔም እንዳንተ ጤነኛ ሳለሁ በጭንቀት ዐበድሁ ያልሁ ሰው ነኝ ። |
| ፫ኛ ዕብድ | አ ! አ ! አ ! ከም አን ! አይል ኪል ሒም ። |
| ፲ኛ ዕብድ | ሐራሾ ! |
| ተዘራ | እሺ ቆዩኝ። ታዲያ የውላችሁ ሲያሠቃዩኝ..... |
| ዕብዶች | (ደረታቸውን እየመቱ ) እኔን ! እኔን ! ወንድማችንን አሞት ! |
| ተዘራ | ቆዩ ደኅና ነኝ ። በፖለቲካ ተከ . . |

፩ኛ ዕብድ ዋልካ ? እኔን ! ዋልካ ጭቃ አምሮህ ?

(ደረቱን እየመታ) ዋይ! ዋይ ! አልሰማህም ወይ ዋይ ! ዋይ ! የኛ ዘንካታ አይደለህም ወይ ! (አሁንም ጥርሱን እንደውሻ አግጥጦ ይቀርበዋል ።)

ተዘራ ቆየኝ እኔም ዐውቄ ያበድሁ ነኝ !

፫ኛ ዕብድ ከም አን ብራዘርስ ሌትስ ኪል ሂም (ወደ ተዘራ ይሮጣል ። ዕብዶች በሙሉ ተዘራን ይ ከቡታል ።)

ዕብዶች ሆ ! ሆ ! ሆ ! ! (ይሸከሙታል ።)

ተዘራ (በጭንቀት) ቆዩኝማ ! (በግሮቹና በጆቹ አን ጠልጥለው እንደ ጅው ጅው ይጫወቱበታል ።) ኧረ እባካችሁ ገደላችሁኝ ! (ወደ ላይ አውጥተው በወለሉ ላይ ይጥሉታል ። ) ዛሬ ሞትሁ ! (እንደገና ያነሡና ተሸክመው እያን ገላቱት ይጨፍራሉ ።)

፩ኛ ዕብድ ተደሰት ዛሬ ተደሰት ። ያን ጊዜ ሚስት ሳገባ የዘፈንኸው ትዝ አይልህም ?

፩ኛ ዕብድ ሔል ዊዝ ዛት ብላዲ ሲንግ !
(ይዘፍናል ።)

፫ኛ ዕብድ ዛሬ ሠርጌ ነው ። ለዕንግዳችን መጠጥ አም ጡለት ። ሰማህ ወይ? ቶሎ አምጡለት ።

፬ኛ ዕብድ ሻምፓኝ ላምጣ ? ዊስኪ ?

ዕብዶች ሁሉ ሻምፓኝ ! ሻምፓኝ ! ሻምፓኝ ! አምጡለት !



(ለብቻው ገለል ብሎ ይቆይና አንድ የሽንት ፖፖ ይዞ ይመለሳል) ።

፪ኛ ዕብድ ይኸው ሻምፓኝ ! ብርጭቆውም በኮረንቲ ነው የታጠበው ።

፩ኛ ዕብድ ምግብም አልበላኮ ! ከጮማው አምጡለት ። (አንድ ዕብድ አንዳች ነገር ያመጣል ። ሁሉም ከበው እያንገላቱ ያጐርሱታል ።)

ተዘራ እንትፍ ! እንትፍ ! እንትፍ ! እንትፍ ! እንት ኑን አበሉኝ ! እንትፍ !

፩ኛ ዕብድ እኔን! እኔን! በርበሬው አስነጠሰው! ለምን ሚጥሚጣውን አበዛህበት ? በል አሁን ሻም ፓኙን አጠጣው ።

፪ኛ ዕብድ (ፖፖውን ወደ ተዘራ አፍ እያቀረበ) ይኸው ጌታዬ !

ተዘራ (እንደነሱ ለመሆን እየሞከረ) ጠገበሁ ። ጠገ ብሁ ፤ በቃኝ ።

፩ኛ ዕብድ ሳትቀምሰው ? በሞቴ እቺን ! (ሌሎች ዕብ ዶች ተዘራን አስጨንቀው ሲይዙለት ፖፖ ውን ከአራተኛው ዕብድ እጅ ተቀብሎ ይግ ተዋል ።)

ተዘራ (በከፍተኛ ጩኸት) አ! ሽንቱን አጠጡኝ ወይ እናቴ ለምን ፈጠርሽኝ! እንትፍ ! ባህ! አክ! ኧ ! ኧ ! ደኅና ነኝ አላበድሁም ! አውጡኝ ! ብትፈልጉ አውጡና ግደሉኝ! (ዕብዶች ይብ ሱን ያንገላቱታል ።)

፩ኛ ዘበኛ የት አባቱ ! ልክ ገባ !

፪ኛ ዘበኛ — እናውጣው !

፩ኛ ዘበኛ — ቆይ ጥቂት ያቅምሱት ።

፪ኛ ዘበኛ — በቃ እናውጣው ፤ ይገድሉታል ።

፩ኛ ዘበኛ — ይበሉት !

ፈረደ — (ከሌላ ክፍል ድምፁን ከፍ አድርጎ) አይ እናንተ ግፈኞች አሁን የምትሠሩት የሰው ሥራ ነው?

፩ኛ ዘበኛ — ዋ ! ዝም በል ። እምቢ ካልህ አንተንም እጨምርኻለሁ ።

ፈረደ — እታደርግምና ነው !

፩ኛ ዘበኛ — በቃ ዝም በል !

ተዘራ — (እጅግ በተጨነቀ ድምፅ) እሪሪሪ ! ገደሉኝ! (ሁለቱ ዘበኞች ወደ ዕብዶች ክፍል በር በይ በልጥ ይጠጋሉ ።)

፩ኛ ዘበኛ — ኮረንቲ መጣ !

ዕብዶች — ኮረንቲ ክፉ ! ኮረንቲ ክፉ ! (ተዘራን ትተው ወደ ኋላ ይሸሻሉ ። ተዘራ እየሮጠ ወደ በሩ ይጠጋል ።)

ተዘራ — (ለዘበኞች) ስለ ወንድ ልጅ አምላክ ፡ ከዚህ አውጡና ግደሉኝ ። (ዘበኞች ተዘራን ካወጡ በኋላ የዕብዶችን ክፍል በር የኋ ሊት ይቆልፉና የተዘራን እጆች በሰንሰለት ያሥራሉ ። ከዚያ ወደ ፈረደ ክፍል ሔደው በሩን ይከፍቱና ተዘራን ወርውረው ያስገ ቡታል ።)



፩ኛ ዘበኛ — በቃ! እዚህም አንድ ነው እንጂ ዕብድ አለ ልህ !

ፈረደ — ተሳደብ አንተ እንስሳ !

፩ኛ ዘበኛ — ዋ ! በግንባርህ አገባብኻለሁ ።

ፈረደ — ወይድ! ለሐጫም! የማይቀረውን ሞት ፈርቼ ያንተ ልሐጭ መትፊያ አልሆንም ። ውሻ !

፩ኛ ዘበኛ — (ጥይት እያቀባበለ) እንዴት አንተ ?

ፈረደ — ንፍጥ! ተኩስ !

፪ኛ ዘበኛ — (እሱም ጥይቱን አቀባብሎ ለጓደኛው) በቃ! እንዴ! ማነው እስከዚህ ቀራጭ ፈላጭ ያደረገህ ? በቃህ ተመለስ !

፩ኛ ዘበኛ — እንዴት ?

፪ኛ ዘበኛ — እንጃልህ ! በናንተ በናንተ ሰበብ እንዴት ሁላችን ከወገኖቻችን ጋር እንቆራረጥ ?

፩ኛ ዘበኛ — አሁን ብደፋው ምን ልታደርግ ?

ፈረደ — (በቍጣና በእልክ ወደ መስኮቱ እየተንጠራራ) ይድፉባህ ! አንት አህያ !

፪ኛ ዘበኛ — ዝም ይበሉ ጌታዬ! እኔ አለሁ ። እስኪ የም ትሠራውን ልይ ! (ፈንጠር ብሎ ይቆማል ።)

ተዘራ — (ለፈረደ) ጌታዬ! ተረፍሁ ስል በርስዎ ሰበብ ደሞ ልሞት ነው ? (ዘበኞች በሩን ይዘጉና ሳይነጋገሩ ይሔዳሉ ።)

ጌታዬ! አፍዎን ቢያሳርፉ ይሻላል ። ሁላችንን እንዳያስጨርሱን ።

ፈረደ (ለተዘራ ) ዝም በል !

ተዘራ (በወለሉ ላይ በልቡ ይዘረረራል ።) ይህን ሁሉ ሁኜ ላልድን? አይ እናቴ! ምነው ባትፈጥሪኝ!

ፈረደ እናትህ ናት እንዴ የፈጠረችህ ?

ተዘራ ታዲያ ማን ነው ?

ፈረደ እግዚአብሔር ነዋ!

ተዘራ እሱማ አዳምንና ሔዋንን ፈጥሮ ፣ ብዝኁ ወተባዝኁ ወምልዕዋ ለምድር ብሎ ከዚያም በርግማን ብላ በላበ ግንባርህ ብሎ ለቀቀና ይቀልድብናል ። አይ አንቺ ዓለም ! ስንቱ ሸናብሽ ስንቱ ተሸናበት!

ፈረደ እሺ ፤ የሆነውስ ሆነና ወደ ዕብዶች ክፍል ያገቡህ ለምንድን ነው ?

ተዘራ በዳኞች ፊት እንዳለሁ ምናልባት ዕብድ ነው ብለው በነፃ ቢለቁኝ ብዬ ዕብድ ለመምሰል ሞከርሁ ። ይባስ ብለው እንዲህ ሠሩኝ ፤

ፈረደ አዬ ! አንተስ ምንህሞኝ ነው ?

ተዘራ ሁለመናዬ ! (ፈረደ ፈገግ ይላል ።)

ፈረደ ለመሆኑ ዋናው ጥፋትህ የተባለው ምን ነበር ?

ተዘራ (በፍርሃት) ጃንሆይን ማማት ።

ፈረደ ምን ብለህ አማህ ?



ተዘራ ኧረ እኔ ምኑንም አላውቀው ፤ ሰክሬ ነበር ።

ፈረደ እሳቸውን ሰድበህ ነው እነእጅሬ ይራሩልኛል ብለህ ያሰብህ ?

ተዘራ እኔማ መሰለኝ !

ፈረደ ተሳስተኻል ። አሁን የምመክርህ እዚሁም ቢሆን አፍ ጠባቂው ብዙ ነውና በጣም እንድትጠነቀቅ ነው ።

ተዘራ እዚህም ? ካሠሩ ወዲያ ምን ሊሠሩ?

ፈረደ ይበልጥ ለማሠቃየት ።

ተዘራ አሁን ይህ ሁሉ ጭካኔ ምን ይሠራላቸዋል ?

ፈረደ የሰው ሥቃይ ምግባቸው ነው ።

ተዘራ ይገርማል ።

ፈረደ በጣም ተጠንቀቅ ፤ አረመኔዎች ናቸው ።

ተዘራ እንዲያው እርስዎስ እንዴት ኖሩ ?

ፈረደ እየተሠቃየሁ ።

ተዘራ ከታሠሩ ስንት ዓመትዎ ነው ?

ፈረደ ዘጠኝ ዓመት ሆነኝ ።

ተዘራ አዬ መከራዬ! እኔንም ይህን ያህል ያሠሩኝ ይሆን ?

ፈረደ አይ! አይመስለኝም ። ቀላል የአፍ ዕልፊት ከሆነ እስከዚህ አያከብዱብህም ። ለመሆኑ ስድቡ ምን ነበር?

ተዘራ — ብርና ወርቁን ውጭ አግዞ ጨረሰው ፤ ጆከር ፣ ጨቋኝ ፤ ብለኻል ነው ያሉኝ ።

ፈረደ — አዎ ! ለነሱ እጅግ ከባድ ነው ። ግን ቢሆ ንም እስከዚህ አያከብዱብህም ።

ተዘራ — ኧረ እንዳፍዎ ያድርግልኝ !
(የፀሐይ ጨረር ቀስ እያለ ወደ ክፍሉ ይገ ባል ።)

ፈረደ — መበርታት ነው ፤ ብዙ አትርበትበትላቸው ።

ተዘራ — እሺ እሞክራለሁ ።
(በድንገት ሁለት ዘበኞች ይመጡና የክ ፍሉን በር ይከፍቱታል ።)

፩ኛ ዘበኛ — ተዘራ !

ተዘራ — (በፍርሃት) አቤት !

፩ኛ ዘበኛ — ና! ውጣ !
(ተዘራ በፍጥነት ይወጣል ። ሁለተኛው ዘበ ኛና ፈረደ በመስኮቱ በኩል የአንገት ሰላ ምታ ይሰጣጣሉ ። ሁለቱ ዘበኞች በሩን ቆል ፈው ተዘራን ይዘው ሲሔዱ መጋረጃው ይዘጋል ።)



## ፩ኛ ፡ ንዑስ ትርእይት ።

በሦስተኛው ቀን ማምሻ ፡ ቦታው ያው የፈ ረደ ክፍል ነው ። ዕብዶች ሲንጫጩ ይሰማል ። ተዘራና ፈረደ በክፍሉ ውስጥ ተቀምጠው ያወጋሉ ።)

ፈረደ — ኧረ ተሻሽለዋል ። እኔስ ላደፋፍርህ ብዬ እንጂ እንዲህ በቀላሉ ያደርጉልኻል አላ ልሁም ነበር ። ሁለት ዓመት ? ምን አላት? ሁለት ቀን ማለት ናት ። ይህን ያህል ጊዜማ! ፍርድ ቤት ሳያቀርቡም ያሥራሉ ። ብቻ አሁንም የምነግርህ ቀለለልኝ ብለህ እንዳ ትሞኝ ነው ። ተጠንቀቅ ። ሊጨምሩም ይችላሉ ።

ተዘራ — እሱንስ እሺ ፤ የሥር ቤቱ ሹምም ነግረው ኛል ።

ፈረደ — እሱም አነጋገረህ እንዴ ?

ተዘራ — (እየቃበዘ) አዎ! ስሞኑንም እየደጋገሙ አነጋግረውኛል ።

ፈረደ — አትመነው ።

ተዘራ — አይዞህ ብለውኛል ።

ፈረደ — መሣሪያ ሊያደርግህ ፈልጎ ይሆናል ። ለመ ሆኑ ስለኔ አልጠየቀህም ?

ተዘራ — (ቅር እያለው) አይ! ጥቂት ጥቂት ነው ።

ፈረደ — በጄ !

(የወህኒ ሹሙ ሁለቱን ዘበኞች አስከትሎ በድንገት ይደርሳል ።)

**የወህኒ ሹም** አንተ ወንበዴ ጥቂትም አይበርድልህ? ደግሞ ሰውዬውን የምትሰብከው ለምንድን ነው?

**ተዘራ** (በችኮላ ተነሥቶ) ጌታዬ ወድጄ አይደለም ። እዚህ ካገባችሁኝ ጀምሮ ስብከቱና ስድቡ ጆሮዬን ሊቆርጠው ደርሷል ። ግን ቀደም ሲል ነቅቼ ነግሬዎታለሁ ።

**ፈረደ** ዝም በል ! ቀፎ! ምንህ ይሰበካል ደሞ ።

**ተዘራ** አዋ! ይኸ ወንበዴ ሊሰድበኝ ነው?

**ፈረደ** ምንህ ይሰደባል ደግሞ ?

**የወህኒ ሹም** ዝም አትልም ?

**ፈረደ** የፈለግኸውን ሥራ!

**የወህኒ ሹም** ግቡና እጅ ከወርች ጠፍሩልኝ! (ሁለቱ ዘበኞች የጅ ሰንሰለትና እግር ብረት ይዘው ይገባሉ ። ተዘራ ይወጣል ። ዘበኞች በፊት የፈረደን እጆች ያሥራሉ ። ቀጥለው እግሮቹን ያሥሩና ከዚያ ወገቡ ወደታች እስኪታጠፍ እጆቹን ወደታች ስበው ከግሮቹ ጋር ያሥሯቸዋል ።) አጥብቅ ! (ዘበኞች ይቀጥላሉ ።) በለው ! አጥብቅ !

**፩ኛ ዘበኛ** በደንብ ጠብቋል ።

**የወህኒ ሹም** ይኸ ነው መድኃኒቱ !



**ፈረደ** ደደብ አረመኔ ጀግንነት አይምሰልህ !

**የወህኒ ሹም** ዋ ! ብታርፍ ይሻልኻል ።

**ፈረደ** ከዚህ ወዲያ ምን ልታመጣ ?

**ተዘራ** ኧረ ይህ አቅሙን አያውቅ ! ቢገድሉህስ?

**የወህኒ ሹም** እንጃ ! (ለተዘራ) አይዞህ! ሁለት ዓመትም አትታሠር! ለሐምሌ ፲፮ ማለት ለጌቶቹ የልደት በዓል ፤ ወይም ለጥቅምት ፳፫ ማለት ለጌቶቹ የዘውድ በዓል አስፈታሻለሁ ። (ተዘራ ያጐነብስና የወህኒ ሹሙን ጫማ ለመሳም ይሞክራል ። የወህኒ ሹሙ ለመግደርደር እየሞከረ ዝም ብሎ ያስመዋል ።) ግዴለም! ግዴለም! ቀና በል! በሥራህ ነው የምረዳህ ! (ለሁለቱ ዘበኞች) ሰማችሁ ወይ ?

**ዘበኞች** አቤት ! አቤት!

**የወህኒ ሹም** አሁን ወደ ሕክምና ክፍል ውሰዱና ደኅና ክፍል ስጡት ።

**፩ኛ ዘበኛ** ሁሉም ተይዟል ጌታዬ!

**የወህኒ ሹም** እንዱን አስወጡና ስጡት !

**ዘበኞች** እሺ ጌታዬ ! እሺ !

**የወህኒ ሹም** የዚህን ወንበዴ ግን መብራቱን አጥፉበት ! (የፈረደን ክፍል መብራት ያጠፉታል ።) በሉ ቆልፉና ነገ ጠዋት ወደ ጨለማ ክፍል እንድትወስዱት !

**ዘበኞች** እሺ ጌታዬ ! እሺ !
(ዘበኞች በሩን ሲቆልፉ መጋረጃው ይዘጋል ።)

## ፳፫ ንዑስ ትርኢት ፡፡

ጊዜው ከጧቱ አምስት ሰዓት ፤ በታው ያው ወህኒ ቤቱ ሁኖ በፈረደ ክፍል ፊት ለፊት የፍርድ ቤቱ ሰብሳቢ ዳኛ የወህኒ ቤቱ ሹም ሁለቱ ዘበኞች ተዘራና ሌሎች ብዙ ሰዎች ቆመዋል ፡፡ ሁለቱ ዘበኞች ወደ ፈረደ ክፍል ከፍተው ገብተው በትኅትና ሰላምታ ከሰ ጡት በኋላ አሁን ተሻሽሎለት የሚታየ ውን እሥራት ይፈቱለታል ፡፡

ሰ. ዳኛ — (ወደ መስኮቱ ቀረብ ብሎ) ይውጡ ጌታዬ ! ከእሥራት ተለቀዋል ፡፡

ፈረደ — (በጥርጣሬ እያመነታ ) ማን ፈታኝ ?

ሰ. ዳኛ — ለውጥ ፈታዎ !

ፈረደ — አዬ ! ይህንንስ አላምንም ፡፡

ሰ. ዳኛ — ይመኑኝ ጌታዬ !

የወህኒ ሹም — ደስ ይበልዎ አገርዎ በመለወጥ ላይ ትገ ኛለች ፡፡ የጭቆና አገዛዝ አከተመ ፡፡

ፈረደ — (አሁንም ባለማመን) ኧረ እንጃ !

የወህኒ ሹም — እኔንም አያምኑኝም ? መቼም ያለፈውን አገዛዝ ምን ያህል እጠላ እንደነበር ዋናው ምስክሬ እርስዎ ነዎት ፡፡ ተጨቁነን ! (ፈረደ ግር ብሎት ይስቃል ፡፡ )

ፈረደ — (ፈገግ እንዳለ) እናንተም ተጨቁናችሁ ነበር?



የወህኒ ሹም — የጭቆና ጭቆና እንጂ ! ሰው እሠሩ እየ ተባልን ! ይልቁንስ ይውጡ !

ተዘራ — አይወጡም እንዴ ! ርስዎ ደሞ ኃግርትዎ አይለቅዎትም ፡፡

ፈረደ — እኔኮ የሁላችሁም ንግግር አልገባኝ ብሎ ነው ፡፡ (በዝግታ ይወጣል ፡፡)

ሁሉም — እንኳን ደስ ያለን ! እንኳን ደስ ያለን ! (እንገቱን እያቀፉ ይስሙታል ፡፡)

ፈረደ — (ከፈገግታ ጋር) ቀን ሁኖ ፊታችሁን በላይ እኔስ እዚህ ያሉት ዕብዶች የመጡብኝ መስሎኝ ነበር ፡፡

ሰ. ዳኛ — ለምን ? ማመን አቃተዎት እንዴ ? ኃይለ ሥላሴ የማይደፈር አምላክ መሰለዎት እንዴ ?

(ፈረደ በትዝብት ይስቃል) እውነቴን ነው ፡፡

የወህኒ ሹም — (በሥጋት) እስኪ ቀስ ይበሉ ፡፡

ሰ. ዳኛ — እንግዲህ በቅቶት ምን ይሆን ብለህ ? ግን ይነሣ ይሆን ? የሱ ነገር አይታወቅምኮ !

የወህኒ ሹም — አይታወቅም ፡፡

ሰ. ዳኛ — (እሱም ሠግቶ) እሱስ እውነትህን ነው ፡፡ (ጥቂት አስቦ) እንግዲህ በቅቶታል እባ ክህ !

የወህኒ ሹም — ያም ሆነ ይህ አሁን ለነሱ ወረቀቱ ይነ በብላቸው ፡፡

ሰ. ዳኛ (በጁ ይዞት የቆየውን ወረቀት እየተመለከተ) እሱስ እሺ! (ለማንበብ ይዘጋጃል ። ሁሉም ፀጥ ይላሉ ። ሰብሳቢ ዳኛ ንባቡን ይቀጥላል ።) ያለፈው ካቢኔ ለኢትዮጵያ ሕዝብ የተጣለበትን ኃላፊነት ሁሉ ዘንግቶ ሕዝቡን በርኀብ በወሀ ጥማት በብርድና በሥቃይ ሲያንገላታው ሲያምታታው ሲወግረውና ሲሰቅለው የቁም ስቅሉን የምኝት ገድሉን ሲያሳየው ከመቆየቱ በላይ ይህን የሕዝቡን እንግብጋቦት ቁም ስቅሉን ውርደትና የልብ ራሮቱን እያዩ ለመታገሥ ያልቻሉ ተቆርቋሪዎችን ሁሉ በወህኒ ቤቶች በማጐር በጥይት በመውገርና ከሀገራቸው በማስፈንጠር በግዞት በማንገላወድና ራሳቸውን በማወላገድ ሲያሠቃያቸው መኖሩ ለማንም ቢሆን እንደ ሌሊት ኮከብና እንደ ቀን ፀሐይ ግልጽ ከመሆኑም በቀር እንደ ዕንግዳ ደራሽና እንደ ወሀ ፈሳሽ በሆነው ማዕበላዊ ለውጥ የተሽቀነጠሩትና የተንጠረጠሩት የድሮ ግፈኞች ሲጉላሉ እነዚህ ተቆርቋሪዎችና የፖለቲካ ጠበብት እንዲፈቱ ታዟል ። ያለፈው ካቤኔ ተወግዟል ።

ዴስ ይበላችሁ ተፈታችኋል ። »

(ይጨበጨባል ። የወህኒ ሹሙ ደግሞ ለመናገር ይዘጋጃል ፤ የሚናገረው በቃል ነው ። )

«አሁን ክቡር ብላታ ሁሉንም የጨረሱት እንደመሆኑ መጠን ምንም ልጨምርበት



አልችልም ። ሆኖም ባለፈው የደረሰብንን ጭቆና መከራ እንግልት ሥቃይ መበሳጨት መቆጨት መቆርቆዝ መወገዝና መደንገዝ መብላላትና መጉላላት መደናጐርና መተሣሠር መቀበጣጠርና መቀባበር የምፈልግ ከመሆኑ በላይ በመከራዊው ዘመን ላይ እነዚህን ያገር ተቆርቋርያን የፖለቲካ እሥረኞች ሁሉ እንደምን ባለ የሀገር ፍቅር ወንድማማችነት ይዘን በመርዳት በማፅናናት በመደገፍና በመደጎም ስላቆየናቸው ከዚህም በቀር ክቡር ሕይወታቸው እንዳይቀጭ በመጠበቅ ያደረግነውን መሥዋዕትነት ሁሉ በኔና በሥራ ጓደኞቼ ስም ሆኜ ሳልገልጸው ባልፍ ጎሊናዬ ይወቅሰኛል ። (ጉንበስ እያለ) ክቡራን የድሮ እሥረኞችና የፖለቲካ ሰዎች ሆይ! ምንም እንኳ እንደናንተ ባንታሠር እኛም በአሣሪነት ስንሠቃይ መኖራችንን ስለ ምታውቁት በጓደኝነት ስታስታውሱን እንደምትኖሩ እምነቴ ዕውቀ ዕመቃት ነው !»

ፈረደ አይ ኢትዮጵያ ! ለመሆኑ ከዚህ ሁሉ ጮሌ ጋር ሁኖ ነው እውነተኛ ነገር የሚሠራው ?

የወህኒ ሹም እንዴት ?

ፈረደ አሁን አንተ ለኢትዮጵያ ተቆርቋሪ ነበርህ?

የወህኒ ሹም ታዲያ ምን ነበርሁ ?

ፈረደ አሳማ ።

የወሀኒ ሹም (በቍጣ) እንዴት አንተ ? ምንስ ቀኑ ላንተ ቢሆን ትሰድበኝ ?

ፈረደ እኔ አልተሳደብሁም ። ቀኑ ያንተ ነው ያለ ኸውም ውሸት ነው ።

ተዘራ እውነት ነው ፤ ቀኑ የኛ ነው ! እኛ ደክመን ተሠቃይተን ባመጣነው ለውጥ ታዲያ ማን ሊፈንጭበት ?

የወሀኒ ሹም እኮ ! ረጋ በሉ ።

ተዘራ ባንረጋስ ? ዛሬም እንዳለፈው ጊዜ ?

ፈረደ እባክህ ተዋቸው ይሒዱ !

ተዘራ ዛሬማ ወደህን!

ሰ. ዳኛ አሁንም እኮ ሥልጣን አለን ።

ተዘራ እንኳን አንተ ጌታህም ሥልጣኑን አጥቷል ።

ሰ. ዳኛ አንተ ! እኛምኮ የለውጡ ባለቤቶች ነን። ያለፈውን መንግሥት ስናብጨቀጭቀው የኖርንኮ እኛ ነን ።

ተዘራ ጉድ ነው!

የወሀኒ ሹም ለመሆኑ አንተ ምን ነኝ ልትል ነው ? የኔ ሰላይ ሁነህ አልነበረም ?

ተዘራ (በዕፍረትና በቍጣ) እኔ ? ቀጣፊ ! ቆይ በጋዜጣና በሬዲዮን ድራሽህን ባላጠፋው ! ቀጣፊ ! (ተዘራ በፍጥነት ወደ ውጭ ይጓዛል ።)



የወሀኒ ሹም አሥረው ነበር እኮ !

፩ኛ ዘበኛ (ኮስተር ብሎ) አይቻልም ።

የወሀኒ ሹም እንዴት ?

፪ኛ ዘበኛ (ጠመንጃውን እያቀባበለ) የለውጥ አዋጅ ብትሽር ራስህ ትታሠራለህ !

የወሀኒ ሹም እኔን?

፪ኛ ዘበኛ ልክ ነው ። (ለፈረደ) ጌታዬ ይሒዱ ፤ እንኳን እግዚአብሔር አወጣዎ !

ፈረደ እሺ ! እኔስ እሔዳለሁ ! ግን ሰዎች እምነታቸውን ሁሉ እንደ እስስት ቀለም በቀላሉ ሲለዋውጡት ሳይ ተስፋ እቆርጣለሁ ።(የወሀኒ ሹሙ ዳኛውና ሁለቱ ዘበኞች ሲቀሩ ፈረደና የተፈቱት የፖለቲካ እሥረኞች ጉዞ ይጀምራሉ ።)

ዕብዶች (ከሩቁ) አ ! አ ! አ! እኛንስ አትፈቱንም ? እኛምኮ ፖለቲከኞች ነን ! (ቀስ እያለ መጋረጃው ይዘጋል ።)

ለሁሉ pdf

www.binyamhk.wordpress.com

# ትርእይት ፬ ።

ጊዜው ከጠዋቱ አምስት ሰዓት ገደማ ወሩ ነሐሴ ፲፮ ዓ. ም. ቦታው የጋዜጠኛው ጉርፉ ቢሮ ። የሰፊው ቢሮ ወለል በአረንጋዴ አበባ ምንጣፍ የተሸፈነ ሲሆን አያሌ ሰዎችን ባንድ ጊዜ ለማስተናገድ የሚችሉ ብዙ ሶፋ ወንበሮች አሉበት ። አቶ ፈረደ ፈንጠር ብሎ በአንድ ወንበር ላይ ተቀምጧል ። ረጂም ግራጫ ካፖርቱን እንደለበሰ ሲሆን ጥቂት ረዘም ያለ ከዘራውን በሁለት እጁ ቆም አድርጎ ይዞ ወለሉን በጽሞና ያስተውላል ። አቶ ተዘራና ከበደች ጐን ለጐን ተቀምጠዋል ። ተዘራ በጣም የጸዱ ጉርዳጉርድ ልብሶች ለብሷል ። መጋረጃው ሲከፈት ጋዜጠኛው በጠረጴዛው ጐን ካሉ ሁለት ቴሌፎኖች አንዱን ይዞ በመነጋገር ላይ ነው ።

ስልኩ ወዲያው ይደውላል ። ጉርፉ ያነሣል ።

ጉርፉ — ሐሎ ! አሎ ! . . . እሺ ! ማን ልበል ጌታዬን ?. .አኬ ! . . . .አኬ . . .ካሁን በፊት ተነግሮልዎታል አይደለም ? . . እሺ ፤ ከሰኞው እቀርብልዎታለሁ ። . . ዛሬ ብዙ ሰዎች ስላሉ ነው ። . . አንደኛው እጅግ የታወቁት የፖለቲካ ተጋዳይ አቶ ተዘራ ናቸው ።. . በቀደም ለታ በሬዲዮና በቲቪ. የሰጡትን ታሪክ ስሙት አይደል ? . . . .የሚደንቅ የሚገርም ነው ። . . ሰው ጥኑ ፍጥረት ነው። እኛ ብዙ ሳናውቅ ስንቱ ቁም ስቅሉን ያይ ኑሯል ! . . . እሺ ፤ አሁን ሥራ ስለበዛብኝ ነው . . .ነው ! ከሰኞው ብቅ ይበሉ ! ምንጊዜም አለሁ ። . . .ጤና ይስጥልኝ ! (ስልኩን ይዘጋና ወደ ዕንግዶቹ ይመለከታል ።) ስንቱ ይሠቃይ ኑሯል እባካችሁ !

ተዘራ — (ኩርፊያ ያለበት በሚመስል ድምፅ) እሱ ማን ነው እኛ የማናውቀው የፖለቲካ እሥረኛ ?

ጉርፉ — ፊታውራሪ ዘነበ ይባላሉ ።

ተዘራ — ፊታውራሪ ብሎ የፖለቲካ እሥረኛ እናንተ ታውቃላችሁ ።

ጉርፉ — እንዴት ?

ተዘራ — በግፍ ሳይተባበር ማን የፊታውራሪነት ማዕረግ ይሰጠዋል ?

ጉርፉ — ምክንያቱ እንዴት ይታወቃል ? እንግዲህ ሁሉም የሚታወቀው ራሳቸው ታሪካቸውን ሲናገሩ ነው ።

ተዘራ — (ራሱን እየነቀነቀ ) አትመኗቸው ! ዋሾውና ጉረኛው በዝቷል ።

ጉርፉ — እሺ ፤ አሁን ስለርስዎ የቀረ ታሪክ እንነጋገር ። ባለፈው ጊዜ የተነገረው መቸም አገሩን ሁሉ አስደንቆታል ።

ተዘራ (በኩራት ከወንበሩ ላይ እየተመቻቸ) አዎ ፣ ገድሌ ብዙ ነው ።

ጐርፉ (የማስታወሻ ደብተሩንና ብርዑን ይዞ) ታዲያ አቶ ተዘራ የሥር ቤት ኑሮዎ እን ዴት ነበር ?

ተዘራ አዎ ! በገባሁበት ጊዜ የሆነውን ቀደም ሲል ተናግሬዋለሁ ። ያ ሁሉ መከራ ከደረሰ ብኝ በኋላ በአንድ ጨለማ አንድ ሰው ብቻ በምታስቀም ክፍል ውስጥ አስገቡኝ። ላይ ታቹ ስሚንቶ ነው ። መዝጊያውን ዘግ ተው በ15 የተደራረበ ልዩ ልዩ ቁልፍ ቆለ ፉት ።

ጐርፉ (በማቋረጥ) ይቅርታ አቶ ተዘራ ! ከውስጥ ሆነው ሲዘጋብዎት ቁልፎችን እንዴት ቆጠ ሯቸው ?

ተዘራ (በማማታት) ይህን የማይረባ ጥያቄ ተወውና ይልቁን ታሪኩን ስማ

ጐርፉ (ደንገር ብሎት) እሺ! . . . .

ተዘራ (በመሻማት) ታዲያ በዚያ ክፍል መቀመ ጥና መተኛት ይቅርና ከቆሙበት መንቀሳቀስ አይቻል ። በተለይ እንደኔ ደረተ ሰፊ የሆነ ሰው ግራና ቀኝ ለመንቀሳቀስ አይችልም ። እዚያው በቁም ቀብረው ሁለት ሳምንት አቆዩኝ ።

ጐርፉ ይገርማል ። ለመሆኑ ምግብና ወሀስ እን ዴት ያገኙ ነበር ?



ተዘራ የምን ምግብና ወሀ ?

ጐርፉ ምንም ሳይቀምሱ ለሁለት ሳምንት ?

ተዘራ ምንም !

ጐርፉ ምንም ሳይተኙ ለሁለት ሳምንት ?

ተዘራ ምንም !

ጐርፉ ይገርማል ! በመጨረሻስ ምን ሆኑ ?

ተዘራ (ሳብ ባለ አነጋገር) ምን ሆነ? በኋላ ከዚያ አወጡኝ ። ከዚያ ስወጣ ቆዳዬ ከግድ ግዳው ስሚንቶ ጋር እንደተጣበቀ ፣ እንደ እባብ ቆዳ በዚያው ሙልጭ ብሎ ተገፎ ቀረ ።

ጐርፉ ልብስ አልነበርዎትም ማለት ነው ?

ተዘራ ልብስስ ነበረኝ ሊያስቀረው አልቻለም ። (ስልኩ ይደውላል ።)

ጐርፉ ይቅርታ (ስልኩን ያነሳል) ሔሎ ! እሺ ጌታዬ! . . . አዎ እንቀበላለን ። . . እሺ . .እሺ . . .አዎ! አሁን ብዙዎችን ኢን ተርቪዩ እያደረግሁ ስለሆነ በሌላ ቀን ብቅ ቢሉ ይሻላል! . .አይደለም . . የለም ጌታዬ! በኛ ሥራ ውስጥ ወገን የሚባል የለም ። እሺ ! ካምስት ቀን በኋላ መሆኑ አይደለም? እሺ . . ይምጡ ጌታዬ . . . እኬ ! (ወደ ዕንግዶች በመመለስ ) አሁንስ እኛም ግራ ገባን ። እንቁላል ሰረቆም ፣ የመንግ

ሥት ገንዘብ ሰርቆም በሰዓት እላፊ ተከሰም የታሠረው ሁሉ የፖለቲካ እሥረኛ ነኝ እያለ ግራ አጋባን ።

**ፈረደ** (ለመጀመሪያ ጊዜ ጣልቃ በመግባት) ለምን ከሁሉም ይኸን ሁሉ ዝባዝንኬ ነገር ችላ አትሉትም ?

**ጉርፋ** እኛማ ያለፈውን ግፍ ማሳየታችን ነበሩ!

**ፈረደ** ታዲያ እንደተዘራ ባሉት ውሸታሞች ነው ያለፈው ግፍ የሚገለጽ ?

**ተዘራ** ምን ማለትህ ነው?

**ፈረደ** ሁላችንም ቀዳዶች ነን ።

**ተዘራ** ስለራስህ ብቻ ተናገር !

**ፈረደ** እሺ በል ፤ አንተም የራስህን እውነት ቀጥል!

**ጉርፋ** እሺ ይቅርታ! አቶ ተዘራ ፤ ሥራችንን እንቀጥል !

**ተዘራ** (በኩርፊያ) እሺ ወንድሜ!

**ጉርፋ** (ማስታወሻ ደብተሩን ተመልክቶ) አዎ! በቁመና ከተገነዘቡት የሲሚንቶ ጨለማ ሳጥን ከወጡበት ላይ ነው ያቋረጥነው ። ከዚያ ካወጡዎ በኋላስ የት ወሰዱዎት ?

**ተዘራ** የቆዳዬን መገፈፍ እንዳዩ ብርድ ነውና እንዲህ ያደረገህ ፤ ሙቀት ያስፈልግሃል ብለው ወደ መጥበሻ ቤት አገቡኝ ።



**ጉርፋ** መጥበሻ ቤት ምንድነው?

**ተዘራ** ስለሌላው አላውቅም ፤ እኔን በኮረቲ ምጣድ ጠብሰውኛል ።

**ጉርፋ** የኮረንቲ ምጣድ ምንድነው ?

**ተዘራ** ምን ልበልህ? ዝም ብሎ ያንጨረጭራል ።

**ጉርፋ** ታዲያ በዚያ አቃጠሉዎት ማለት ነው?

**ተዘራ** አንጨቀጨቁኝ! ደሜ በቃጠሎው እየገነፈለ ከምጣዱ ውጭ ሲፈስ ሳይ ያው አለቀልኝ ብዬ ነፍሴን ስቼ ወደቅሁ ።
(ፈረደ ትዝብቱ ገንፍሎበት ለብቻው ያማትባል ።)

**ጉርፋ** ከዚያስ ከምን ውስጥ ጣሉዎት ?

**ተዘራ** እንግዲህ ከዚያ በኋላ አውጥተው ባንድ ቁሻሻና ጠባብ ክፍል ይጥሉኛል ፤ ምን ያህል ቀን እንደቆየሁ ነፍሴን አላውቀውም ።
(ስልኩ ይደወላል ።)

**ጉርፋ** (ለተዘራ) ይቅርታ ጌታዬ ! (ቄጣ ብሎ) ማ! ልበል ጌታዬ ? . እሺ . . (በመስልቸት) እሺ! ጥሩ ነው ። ግን አሁን ከንግዶች ጋር ነኝ ። . . .እሺ እሱማ ነው ! . . ግን ፋታ ማግኘት እኮ አለብን . . .(ካዳመጠ በኋላ ፈገግ ይላል) በነሱ ቋንቋ መናገሬ አይደለም ! . . ሦስት አራት ቀን ያሻናል ! . . በዛኮ ! አዎ! ተሠቃይታችኋል ! ግን . .

አይደለም ጌታዬ !. . . ከሰሞኑ . . . በሚመ ችዎት ቀን . . እኔማ! ሁል ጊዜም እዚሁ ነኝ . . የለም! ጋዜጠኛም ብሆን አሁን ወሬው ሁሉ እኛ ድረስ ስለሚመጣልን ወሬ ፍለጋ አንሔድም . . . አኬ !

ተዘራ (እየተንጎራደደ) ለካስ ማንም በፖለቲካ እየገባ ግራ አጋብቷችኋል ማለት ነው !

ጉርፉ ምን ማለትዎ ነው ፕሮፌሰር ?

ተዘራ ፖለቲካ ለኛ ለፖለቲካ ዐዋቂዎች ብቻ መትተው አለበት ። (ወደ ፈረደ በሥጋት ዘወር ብሎ ከተመለከተ በኋላ) «ሁሉ አረሰ ማን ይሸምት?» የሚመለው ቃል ትዝ አለኝ!

ጉርፉ ግን እኮ ባለፈው ጊዜ መንግሥቱ የወደ ቀው ሕዝቡ በፖለቲካ እንዳይካፈል አድርጎ በጥቂት የፖለቲካ ዐዋቂዎች ብቻ ስለ ተማ መነ ነው ። ፖለቲካ የአንድ ሕዝብ ያልተወ ሰነ ሀብት ነው ይባላል ። እሺ ፤ አሁን ወደ ዋናው ጉዳያችን እንመለስና ከመጥበሻው ቤት ከወጡ በኋላ ምን አደረጉዎት ?

ተዘራ ከብዙ ቀኖች በኋላ ነፍሴን ዐወቅሁ ፤ ራቡ ጥማቱ ተለቀቀብኝ ፤ ግን ማን እህል ወሀ ቢያቀምስ !

ጉርፉ እሺ ታዲያ እንዴት ኖሩ ?

ተዘራ (ወደ ከበደች እያመለከተ) በቃ ! ይች መልአክ የሆነች ሚስቴ አልቅሳም



ጨኸም ለመጠየቅ ተፈቀደላት ። ከዚያ በኋላ ቀልባ አዳነቺኝ ።

ጉርፉ ከመታሠርዎ በፊት ተጋብታችሁ ነበር ማለት ነው?

ተዘራ የሕግ ሚስቴ ናት ፣ በቁንጮዋ ያገባ ኋት ። በቁንጮዋ ፤ ገና እሷም እኔም ለጋዎች ሳለን ።

ጉርፉ ይቅርታ ፕሮፌሰር ተዘራ ፤ ባለፈው ጊዜ ፕሮግራማችን አሥር ዓመት በፈረንጅ አገር እየተዘዋወሩ ሲማሩ መቆየትዎን ነግረውን ነበር ። እንግዲህ ወደ ፈረንጅ አገር ከመሔድዎ በፊት ቢያንስ ቢያንስ በሀገርዎ መቆየት ነበረብዎት ማለት ነው ። ታዲያ በስንት ዓመትዎ አገቡዋ ቸው ማለት ነው? ደግሞስ ውጭ ተምረው ተመልሰው ቁንጮ ያላትን ያሀገርዎ ወጣት ለማግባት ያነሣሣዎ ምንድን ነው ?

ተዘራ (በዕፍረትና በቍጣ) ጉድ ! ለካ የሀገራ ችን ሥራ ሁሉም ተበላሽቷል ! አንተ ጆርናሊዝም እንጂ ፖሊሲዝም አይደለ ህም! ጠይቀኸኛል ፤ መልሱን በቀጥታ መቀ በል ነው ፕሮፌሽናሊዝምህ የሚያዝህ ።

ጉርፉ (በትዝብት ፈገግ ብሎ) እሺ! ፕሮፌሰር! .

ተዘራ ባንተው ቃል ልጠቀምበትና ! ይቅርታ እኔ ፕሮፌሰር ብሆንም ፕሮፌሰር አል ባልም ።

ጉርፉ ለምን ይህን ስም ጠሉት ?

ተዘራ ፊውዳሊዝሙ መንግሥት ይጠላው ስለ ነበር ፤ ከቶ ወይም ኔቨር ተጠቅሜበት አላውቅም ።

ጉርፉ እኒህ እመቤቱስ ለምን ያህል ጊዜ ረዱዎት?

ተዘራ (በታላቅ የውሸት ስሜት ጉንጭዋን እየ ዳሰሰ) ሐያ ዓመት ሙሉ! አንድ ቀን! ከሐያው ዓመት ቀኖች ውስጥ አንድም ቀን! እጇ ከተያዘበት ደቂያ አንድም ቀን ሳትለየኝ ረዳችኝ ።

ጉርፉ (በሽሙጥ) በቆዳው መግፊፊያና በመጥ በሻው ክፍል በቆዩባቸው ሳምንታትም አልተለዩዎት ማለት ነዋ!

ተዘራ ኸ ! (እንደማሰብ ይሞክራል) ግዴለም! ያንን ክፍለ - ጊዜ ቀንሰው!

ጉርፉ (ፈገግ ብሎ) ታዲያ የቀረውንስ እንዴት ረዱዎት ?

ተዘራ አዎ! የወጣትነት ፤ የሙሽርነት ጊዜያችንን ሳንጨርስ በለጋነታችን ገና ጡቷ ሳይወ ድቅ ታሠርሁ ። ከዚያ ሐያ ዓመት ሙሉ ከነንጽሕናዋና ታማኝነቷ እየተንገላታች ስትረዳኝ ቆየች ። ሀብቴን በሙሉ ከመያዛቸው በላይ ስድስት ልጆቻች ንን የት እንዳደረሷቸው ሳይታወቅ አጠፉዋቸው ። ከዚያ ሁሉ ነገር ቢያቅ ታት አረቄ በመለኪያ እየቸረቸረች ስት



ደግፈኝ ቆየች ። ስለዚህ በእውነቱ የርሷም ታሪክ በሚገባ መነገር አለበት ።

ጉርፉ (ወደ ከበደች እየተመለከተ) እሜትዬ! በእውነትም በጣም ተጐድተዋል ። ለመ ሆኑ ልጆችዎ የት የደረሱ ይመስልዎታል?

ከበደች (በዕፍረትና በመደናገር መሬት መሬት እያየች) የቶቹ ልጆቼ?

ተዘራ (በመሻማት) እባክህ ደኅና የረሳችውን ኃዘን አታስታውሳት ። እስኪ ይልቁን ቁም ነገሩን! ከብዬ ፍቶግራፍሽን ይዘ ሻል አይደል? (ወደ ከበደች ቀረብ ይልና ቦርሳዋን ከጐኗ ካስቀመጠችበት አን ሥቶ ይሰጣታል ።) እስኪ እንቺ አውጪ ውና እንስጠው ። (ስልኩ አሁንም ይደ ውላል ።)

ጉርፉ ይኸ ስልክ እኮ! አላሠራኝም ።

ተዘራ ዝም አትለውም!

ጉርፉ ጣጣ እኮ ነው! እንዴት ዝም ማለት ይቻ ላል? (ስልኩን ያነሣል) ሐሎ . .ጤና ይስጥልኝ . .እ! ነው ? . . እሺ ጌታዬ . . እሺ ጌታዬ! . . አሁንም እዚሁ አሉ ። ብቻ አሁን ሥራ ላይ ስለሆን በሌላ ቀን እንድትነጋገሩ ባደርግ ይሻል ይመ ስለኛል ። አዎ ! ካሁን በፊት ዕውቂያ ከሌላችሁ ተገናኝቶ መነጋገሩ ይሻላል . .አዎ ! ከዚህ አይጠፉም ። (ሰዓቱን

እየተመለከተ) ነገ በዚሁ ሰዓት ቢደውሉልኝ . . እሺ! . . ጤና ይስጥልኝ ። (ስልኩን ይዘጋና ወደ ተዘራ እየተመለከተ) የአሁኑ ሰውዬ ያሉኝን ያውቃሉ ?

ተዘራ ያው ባልዋለበት የፖለቲካ ትግል ቀንደኛ ነኝ ለማለት እንጂ ሌላ ምን ይላል?

ጉርፉ የለም እንደዚህም አይደል ፤ ያሉት ። የርስዎን ኢንተርቪዩ በሬዲዮም በቲቪም ስለሰሙና በጋዜጣ ስላነበቡ ከኒህ ታላቅ ኢትዮጵያዊ ጋር አስተዋውቀኝ ነው ያሉኝ ።

ተዘራ (በደስታና በኩራት ተሞልቶ) እውነትህን ነው?

ጉርፉ ልሙት ።

ተዘራ ይኸማ ታላቅ ሰው ነው ። ለመሆኑ ካሁን በፊት ዐውቃቸዋለሁ ነው ያለህ ?

ጉርፉ የለም! አላውቃቸውም ነው ያሉ ።

ተዘራ ረስቶኝ ይሆናል እንጂ አዲስ አበባ ውስጥ ኖሮ ፤ በተለይም የፖለቲካ ስሜት ኖሮት እኔን የማያውቅ እንኳ የለም ። ግን አዎ ! ሐያ ዓመታት ሙሉ ዘግቶብኝ ሲኖር ሕዝቡ ቢረሳኝ ምን ይፈረድበታል ?

ጉርፉ ለምን ቁጭ አይሉም ጌታዬ ?

ተዘራ አሁንማ ልንቀሳቀስ እንጂ ፤ ሐያ ዓመት ተኮድኩጄ ኖርሁ ።



ጉርፉ እሺ አቶ ተዘራ! ያ ሁሉ ሥቃይ የደረሰብዎ ምን ስለሠሩ ነው?

ተዘራ ልገለብጠው ስል ስለተያዝሁ ።

ጉርፉ እንዴት ባለ መንገድ ነው ሊገለብጡ የነበር ? ጥቂት ቢያብራሩልኝ!

ተዘራ በምኑ ይበልጠኛ መሰለህ? በዘርም እበልጠዋለሁ ። በአራቱም አያቴ የነጋሢ ዘር ነኝ ።

ጉርፉ እሱማ ነው! ዝግጅቱስ እንዴት ነበር? ከወታደሩ ክፍልስ ግንኙነት ነበረዎት? ወይም ሌላ ድርጅት ነበረዎት ወይ? ማለቴ ነው ።

ተዘራ በዕውቀትስ ቢሆን ከጥጌ የት ይደርሳል ። እሱ ፈረንሳይኛ ብቻ ያልከሰከሳል ። እኔ ግን እንግሊዘኛ ፈረንሳይኛ ጀርመንኛ ይዲሽ ዳኒሽ ፍሌሚሽ ስዊድሽ ኖርዌጅያን ፤ ሰዋሂሊና ኩሽ ፡ ዓረቢክና ድርቡሽ እናገራለሁ ፡ እጽፋለሁ ፡ አነባለሁ ፡ በጣም ጠንቅቄ ።

ጉርፉ እንዴ ! ተአምረኛ ሰው ነዎትና !

ተዘራ ዓለም ያወቀውን !

ጉርፉ እሺ ጥያቄዬም ጠፋኝ! (ለራሱ ፈገግ ይላል።) እና ሤራዎ ተደርሶበት ነው የታሠሩ ማለት ነው ?

ተዘራ (በችኮላ) አዎ !

ጐርፉ ቢገለብጡስ ኑሮ ከዚያ በኋላ ዓላማዎ ምን ነበር?

ተዘራ እ! እ! ኢትዮጵያን ማሠልጠን ፤ ማሳደግ ፤ ከዓለም መንግሥታት ማስበለጥ

ጐርፉ ማለት ምን ዓይነት መንግሥት አቋቁመው?

ተዘራ እኸ! ኸ! ኸ! እሱ በተቀመጠበት ቦታ ላይ ብቀመጥስ ለወንበሩ ከርሱ እኔ አልከ ብደው መስለህ ?

ጐርፉ ዓለማዎ መንገሥ ነበር ማለት ነው?

ተዘራ አይ ! አይ ! አይ! የምን መንገሥ አመ ጣህ ደሞ! ይኸን ዘመን የጠላው ስም ምን በወጣኝ !

ጐርፉ ታዲያ ምን ዓይነት መንግሥት ለማቋ ቋም ነበር ዓላማዎ?

ተዘራ ሕዝባዊ መንግሥት ።

ጐርፉ ምን ዓይነት ሕዝባዊ መንግሥት?

ተዘራ ጭቅጭቅ አታብዛ! ሕዝባዊ መንግሥት አልሁህ!

ጐርፉ እሺ ፤ ባሁኑ ጊዜ ምን ዓይነት ሥራ ቢሰጥዎ ደስ ይልዎታል?

ተዘራ ያው ሰብሳቢነቱ ነዋ!

ጐርፉ የሚኒስትሮች ምክር ቤት ሰብሳቢ ማለ ትዎ ነው?

ተዘራ ተባረክ ፤ ገብቶኻል ።



ጐርፉ ከሱስ በቀር ሌላ ምርጫ የለዎትም ?

ተዘራ የቋንቋ መድበል በመሆኔ የውጭ ጉዳዩ ንም ብይዝ እጅግ ደስማማኛል ። ግን ሁለቱንም አጣምሬ እይዝ እንደሆነ እንጂ የውጭ ጉዳዩ ብቻ ያንሰኛል ፤ ሆኖም አሁን በቅርቡ የራሴን የፖለቲካ ፓርቲ ስለማቋቁም ያን ጊዜ ሁሉንም እወስናለሁ ።

ጐርፉ ምን ዓይነት ፓርቲ ለማቋቋም አስበዋል?

ተዘራ የመሳፍንት ወገን እንደመሆኔ መጠን ኮንሴርፋቲፍ ፓርቲ አቋቁማለሁ ።

ጐርፉ ፓርቲዎ በምርጫ ቢያሸንፍ ምን ምን ሊሠሩ አቅደዋል?

ተዘራ ያለውን ነገር ሁሉ አፈራርሼ አዲስ አስተዳደር እመሠርታለሁ ።

ጐርፉ ታዲያ ይህ ከኮንሰርቫቲቭ ዓላማዎ ጋር አይጋጭብዎትም?

ተዘራ እሱን ለኔ ተወው ፤ ከኔ ይበልጥ አታው ቅም ። ይልቅስ . . (ከከበደች እጅ ፎቶ ግራፉን ይወስዳል) ይህን የዚች ደግ ወይዘሮ ፎቶግራፍ አውጣልኝ ። ዋነኛው ዓላማዬ ደግሞ ሴቶችን ከወንድ በላይ ማድረግ ነው ። አሁን ፓርቲ ሳቋቁም ዋና ጸሐፊ አድርጌ የምሾምም እርሷን ነው ። (ጐርፉ ፎቶውን ይቀበላል ።)

ጐርፉ — እሺ ፤ በጋዜጣ እንዲወጣ አደርጋለሁ ። ለመሆኑ እሜቴስ ስለፓርቲው ጉዳይ ምን አስተያየት አለዎት?

ከበደች — (በፍጹም ዕፍራና ግራ ገብቷት) እንግዲህ የግብዣውን ዝግጅት አይቼ ነዋ! አስተያየቴን የምሰጠው ።

ጐርፉ — (ፈገግ ብሎ) እግዜር ይስጥልኝ ። (ወደ ፈረደ ይዞራል) ጌታዬ! አቶ ፈረደስ የሚነግሩኝ ብዙ ታሪክ አለ?

ፈረደ — (የከዘራውን ወገብ በሁለት እጁ ጠበቅ አድርጎ እንደያዘ) ብዙ እንኳን አይደለም ።

ጐርፉ — ስንት ዓመት ነበር የተፈረደብዎ?

ፈረደ — ዕድሜ ይፍታህ ።

ጐርፉ — ስንት ዓመት እንደታሠሩ ነው የተፈቱት?

ፈረደ — አሥር ዓመት እንደታሠርሁ ።

ጐርፉ — ሲፈቱ ምን ተሰማዎ?

ፈረደ — ሀገሬም ራሴም ባንድ ጊዜ ነፃ ስንወጣ የተሰማኝን ደስታ መገመት ለማንስ በምን ያስቸግራል?

ጐርፉ — ለምን ነበር የታሠሩት?

ፈረደ — መንግሥት በመገልበጥ አድማ ።

ጐርፉ — በርግጥ ነበሩበት?



ፈረደ — አዎ ።

ጐርፉ — ለመሆኑ አድመኞች የተባላችሁት አገር ወዳዶች ብዙ ነበራችሁ?

ፈረደ — አዎ ! ብዙ ነበርን ፡

ጐርፉ — ከምን ከምን ክፍል የተውጣጣችሁ ነበራችሁ?

ፈረደ — ከወታደሩም ፤ ከሲቪሉም ወገን ።

ጐርፉ — የታሠራችሁት ብዙ ነበራችኋ?

ፈረደ — አዎ ።

ጐርፉ — ስለ ማፈኛውና ስለ መጥበሻው ክፍሎች ያዩት አለ?

ፈረደ — በፍጹም አላየሁም ።

ተዘራ — (ጣልቃ በመግባት) እነሱ የሚጠብሱት እኮ! በጣም የሚፈሩትን እንደኔ ያለ እሥረኛ እንጂ እንደርሱ ያለውን ማንኛውንም የፖለቲካ እሥረኛ አይደለም! ለካ! ሰው ለይታችሁ ማወቅ አትችሉምና!

ፈረደ — (በቍጣና በትዝብት) ዝም በል! ቀዳዳ በማን ፊት ነው የሚቀደደው!

ተዘራ — እሱም (በቍጣና በጩኸት) እንዴት አንተ?

ፈረደ — ወይድ፤ዝም በል! 'ለማያውቅሽ ታጠኚ' አሉ!

ተዘራ — እንዴት?

ፈረደ — እንጃልህ!

ተዘራ — እንዴት? ልትሰድበኝ ነው እንዴ ?
(ጐፊሬውን ያሳደገውና ሽክ ብሎ የለበ ሰው ዶክተር ምትኩ አንበርብር በሩን እንኳኩቶ ዘው ብሎ ይገባል ። ጐርፉ ከተቀመጠበት ብድግ ብሎ ተነሥቶ ሰላምታ ለመስጠት ራመድ ሲል ፈረደ በመጠኑ ብድግ ይልና መልሶ ይቀመጣል ። ዶክተር ምትኩና ጐርፉ በጋለ ስሜት በመጨባበጥ ሰላምታ ይሰጣጣሉ ።)

ጐርፉ — ላስተዋውቃችሁ ። (ወደተዘራ እጁን ዘርጋ አድርጎ) አቶ ተዘራ ወይም ፕሮፌሰር ተዘራ የሚባሉት የፖለቲካ እሥረኛ እኒህ ናቸው። እርሱም ዶክተር ምትኩ አንበርብር የተባለው የታወቀው ተራማጅ ምሁር ነው። (ተዘራና ምትኩ ይጨባበጣሉ ። ጐርፉ ወደ ፈረደ ያመለክታል ።) እርሳቸውም የፖለቲካ እሥረኛ የነበሩ ናቸው ። (ፈረደ ይነሣና ከምትኩ ጋር ይጨባበጣሉ) ሁለቱም ለረጂም ዓመታት በወህኒ ቤት የቆዩ ሲሆኑ (ወደ ተዘራ እያመለከተ) በተለይ አቶ ተዘራ ይሽ ነው ተብሎ የማይገለጽ ሥቃይ ደርሶባቸዋል ። (ወደ ከበደች እያመለከተ) እኒህም ታላቅ አርበኛ የሆኑ የአቶ ተዘራ ባለቤት ናቸው ። ወይዘሮ ከበደች ይባላሉ ። (ተነሥታ ትጨብጠዋለች ።)

ምትኩ — አይ ሲ!



ጐርፉ — ቁጭ በሉ ።(ሁሉም ይቀመጣሉ ።) እሱም ፣ ለአሥራ ስምንት ዓመት አውሮፓ ውስጥ ራሱን አግዞ የቆየ ተራማጅ ምሁር ነው ። አሁን ይኸው ሁለት ተጋዳይ ክፍሎች ለመገናኘት በቃችሁ ።

ምትኩ — (በጣም ቅር እያለው) አዎ! በምንም ቢለ ያይም ለማጀሪቲው ሲሉ ካለፈው ኢ.ስ ብአዊ መንግሥት ጋር ሲጋጩ መቆየቱ መጠናዊ ክሬዲት የማይነፈገው ነው ።

ጐርፉ — ነው ።
(አንድ ገበሬ ወረቀት ይዞ ይገባና እጅ ነሥቶ ይቆማል ። ያነጋገረው ግን የለም ። ሁሉም ጸጥ ብለው ያዳምጣሉ) መቼም ስለወደፊቱ የሀገራችን የፖለቲካ አቋም ውይይት ብታደርጉ ለአድማጮች ከፍ ያለ እንተረስቲንግ እንትን ይሆን ነበር ።

ምትኩ — ከነማን ጋር ?

ጐርፉ — (ወደነ ተዘራ እያመለከተ) ከነሱ ጋር ።

ምትኩ — እሱ እንኳ አይሆንም! ለመሆኑ እምቡጠ—ርዕስ የሆነው ነደ — ፍልስፍና እንዴት አንደርስቱድ ሊሆንላቸው ይችላል? (ፈረደ ምትኩን ትኩር ብሎ ያየዋል ።)

ፈረደ — ወንድም ለመሆኑ የማን ልጅ ነህ ?

ምትኩ — እኔ እንኳን አፍርባቸዋለሁ እንጂ አልኮራባቸውም ። ሆኖም አባት ናቸው ፤ ደጃች አምበርብር ይባላሉ ።

ፈረደ እንዴ ! እንዴ! እንዴት ራሳቸውን መልሰው ወልደዋል እባካችሁ ? እሳቸውንማ በጣም ዐውቃቸው አልነበር !

ምትኩ (በቸልታና በኩራት) አዎ ያውቋቸው ይሆናል ። ብዙ አሽከሮች ነበሯቸው ፤ ብቻ አል ኮራበትም ።

ፈረደ አሽከራቸው እንኳ አልነበርኹም ። ብቻ ዐውቃቸዋለሁ ። እንደዛሬው ደጃዝማችነት ለሣር ቅጠሉ ሳይደርስ ፤ ስማቸው የተጠራ ደጃዝማች ነበሩ ።

ምትኩ ኃይለኛ አርበኛ ነበሩ ይባላል ። ግን አል ኮራበትም ።

ፈረደ እ! እ! አርበኛስ አልነበሩም ፤ ከንጉሡ ጋር ነበር የተሰደዱት ።

ምትኩ (ተናዶ) በቃ አያውቋቸውም ። አልኮራበትም እንጂ ካርበኛ በላይ የሆኑ አርበኛ ነበሩ ።

ፈረደ (ፈገግ ብሎ) ልጄ ፤ ባለፈው መንግሥት ካርበኛ ስደተኛ እጅግ ይበልጥ ይከበር እንደ ነበር አታውቅም ?

ምትኩ ቢሆንሳ! ታዲያ ምንም ባልኮራባቸው አባቴ ከማንም ፈርጣጭ ጋር ይቈጠሩ ?

ፈረደ (በቀልድ) የእምቦሳ ጥጃ ያህል መፈርጠጣቸውን ባላይም ቀድመው ከተሰደዱት ሰዎች አንዱ የነበሩ መሆናቸውን ዐውቅልኻለሁ።



ምትኩ የኔ አባት ?

ፈረደ መቼም ልጃቸው መሆንህን በመልክህም ልረዳ ችያለሁ ። ደጃች አምበርብር ስብስ ቤን ከሆነ የምትለኝ ከማይጨው ጦርነት ከተመለሱ በኋላ ጥይት ማጮህ ቀርቶ ወደ ጠላት ጠጠር ሳይወረውሩ ወደ ባሕር ማዶ መሰደዳቸውን ዐውቃለሁ ።

ምትኩ ምንም አያውቁ ።

ፈረደ (በመታገሥ) እሺ ፤ ይሁንልህ ፤ አላውቅም ። እስኪ አሁንስ ሁሉን እንተወውና ስለቆየህበት አገር አውጋን ።

ምትኩ ምን ያደርግልዎታል ።

ፈረደ ለማወቅ ያህል ።

ምትኩ አዎ! አሁን አዝናለሁ ። በቆየሁበት አገር አስተዳደር አላምንበትም ። ቢሆንም ሆላንድ አምስተርዳም ነበር የኖርሁት ።

ጉርቱ (ጣልቃ ገብቶ) ይቅርታ ስለማቋረጤ ። ምን ይምጣላችሁ ? ንግግራችሁ እየማረከኝ ዝም ብዬ ቆየሁ ። ምን ይምጣላችሁ? (ወደ ከበደች እየተመለከተ) እሜትዬ ! ምን ይምጣልዎ ?

ከበደች (ግራ ገብቷት) ምን ?

ጉርቱ የሚጠጣ ነገር ።

ከበደች (እየተሽኮረመመች) ውስኪ በኮካኮላ ። (ሁሉም ዐፍረው ጸጥ ብለው ይቆያሉ ።)

ተዘራ — ግዴለም አሁን ሙቀት ነው ፤ ቀዝቃዛ ኮካ ኮላ ብቻ ይሁንላት ።

ጕርፉ — (ቸኮል ብሎ) እሺ እናንተስ?

ምትኩ — ቡና ።

ተዘራ — ለኔም ኮካኮላ ።

ፈረደ — የአምቦ ውሀ ።

(ጕርፉ የተላላኪ መጥሪያ ደወል ሲደውል ተላላኪ በሩን ከፍቶ ይገባል ።)

ጕርፉ — (በችኮላና በዝንጋታ) ዊስኪ ከኮካኮላ ጋር ። አ ! ይቅርታ ! (ራሱን በጁ ይመታል።) አንድ ! ኮካ . . አ ! ይቅርታ ሁለት ኮካ ኮላ . . . እኔም ቡና ልጠጣ መሰል! ሁለት ቡና አንድ አምቦ ውሀ ቶሎ አምጡልኝ በላቸው ።

ተላላኪ — (ለጠጥ ብሎ) እሺ ካሉ ምን ቸገረኝ !

ጕርፉ — አ ! እባክህ ቶሎ በልና አስመጣልኝ ።

ተላላኪ — እንዴ ! ቡና ለማፍላት የተቀጠርሁ መሰለዎት እንዴ ?

ጕርፉ — እባክህ ሙግቱን ተወው ጃል ።

ተላላኪ — ለእኩልነት መብቴ መሟገቴ ነውር ነው እንዴ ?

ጕርፉ — (ወደ ዕንግዶቹ በዕፍረት ዘወር ብሎ) አዲዮ አለቅነት ከነሥነ — ሥርዓት !

ተላላኪ — በፈረንጅ ቋንቋ መታማት ጉዳያችን አይደለም ።



ጕርፉ — ኧረ ስለእግዚአብሔር ብለህ አልሰደብሁህም ፤ እባክህ ቶሎ ንገርልኝ !

ተላላኪ — (እየተጀነነ) እሺ ፤ ነገሩ እንኳ የእዝጌርን ስም የምታውቁት ሲጨንቃችሁ ብቻ ነው። ሆኖም እንደርስዎ አይደለሁም ። እሺ ካሉ እነግራለሁ ። (በሩን ከፍቶ ሳይዘጋው ይሔዳል ። ጕርፉ ከቍጣና ከዕፍረት ጋር ተነሥቶ በፍጥነት ወደ በሩ ይሔድና ዘግቶት ተመልሶ ይቀመጣል ።)

ጕርፉ — ይህ ተአምረኛ መብትና ነፃነት እኮ! ጉድ አፈላብን ።

ምትኩ — ለዚህ መድኃኒቱ ከብረት ግድግዳ የጠነከረ ዕመቀ ዕመቃዊ ፓርቲ ማቋቋም ብቻ ነው ።

ጕርፉ — እኮ እሱን ማን ያቋቁመው ?

ተዘራ — እኛው ነና!

ምትኩ — ኼት ! ኼት ! ኼት ! ኖ ! ኖ! ኖ! (ከተቀመጠበት ይነሣል ።) ይህ ፈደላዊ ሃሳብ ነው ።

ተዘራ — ምንድነው ፈደላዊ ?

ምትኩ — ይህ አይደል ጉዱ ! ይህን ሳታውቅ ዘሎ ፖለቲካ ላይ ቁብ !

ተዘራ — አንተን ከገባህም ታምር ነው ።

ጕርፉ — እስኪ ዶክተር ሳትቈጣ ተወያዩበት ።

ምትኩ — (ከተቀመጠበት ተነሥቶ ።) ከነማን ጋር ።

እሺ ፤ ዶክተር ለሁሉም ቁጭ በልና እንወያይ !

ምትኩ — እኮ ! ከነማን ጋር ?

ጉርፉ — እሺ ከኔ ጋር ።

ምትኩ — (መሐረብ አውጥቶ የፊቱን ላብ እየጠረገ) ለዚህ ነው የጠራኸኝ? ለመሆኑ አንተስ ማን ነህ ?

ጉርፉ — የኔን ተወው ግዴለህም ! . . . . .

ምትኩ — (ዐውቆ በመከላተፍ) ባርካ ማዜሪያ! ሚን ጉደኛ አጋርና ባካቹ !

ተዘራ — አገሩም ግራ ገባህ መሰለኝ ።

ምትኩ — ግራ የገባህ አንተ !

ጉርፉ — (ተነሥቶ) ዶክተር እባክህ ስለ እግዚአብሔር ብለህ ቁጭ በልና እንነጋገር ።

ምትኩ — ደሞ የሚን የቄስ ተርሚኖሎጂ አመጣህ ?

ጉርፉ — እሺ ! እሱ ግዴለም ። አላነሣውም ተሳስቼ ነው ።

ምትኩ — እኮ ! ምን ከነማን ጋር እንጋገራለሁ ?

ፈረደ — (በብስጭት ጣልቃ በመግባት) ወንድም ለመሆኑ ሆላንድ ምን ያህል ጊዜ ቆየህ?

ምትኩ — አሥራ ስምንት ዓመት

ፈረደ — ዕድሜህ ስንት መሆኑ ነው ?

ምትኩ — አልጨረጨስኹም ። ሃያ ስምንት ።



ፈረደ — እሺ የሆነውስ ሆነና የጌታዬ ልጅ ፤ ተምረኸው የመጣኸው ምንድን ነው ?

ምትኩ — (በትክክለኛ ቋንቋ) ፖለቲካ ፤ ማለት ፖለቲካል ሳይንስ !

ፈረደ — ሆላንድ ከቆየህ እዚህ የማንም ፈረንጅ ከሚቀልድብን ለምን የወንጂን ስኳር ፋብሪካ የሚመለከት ሙያ ተምረህ አልመጣህም ?

ምትኩ — (በቍጣ) እንዴት? እኔ ኩሊ ሁኜ አገሩን ማን ሊመራው ? እኔ የምፈልገው በግድም በውድም አገሩን መምራት ነው ።

ፈረደ — በማን ፈቃድ ?

ምትኩ — በራሴና በተራማጁ ኃይል ፈቃድ ።

ፈረደ — የቱ ነው ተራማጁ ኃይል ?

ምትኩ — የፋብሪካ ሠራተኛና ተማሪ ።

ፈረደ — በመቶ ዘጠና የሚሆነው የሀገሪቱ ሕዝብ የራሱን ዕድል የሚወስን እሱ መሆኑን አትርሳ ።

ምትኩ — (በጩኸት) አንተ አድኃሪ ! ምኑን ታውቃለህ ! (ፈረደ በፍጥነት ተነሥቶ ይቆማል ።)

ፈረደ — ረጋ በልኮ !

ምትኩ — የምን መርጋት ?

ተዘራ — ወይ ጉድ ! አሁን የናንተው ክርክር ምን ባይ ነው ? ዳሩ አሁን የኔ ፓርቲ ሲቋቋም

ታርፈዋለህ ! የታገልሁ እኔ ! የታሠርሁ እኔ! ምን አገባችሁ ?

**ምትኩ** የሞትሁ እኔ! የተጋደልሁ የተናነቅሁ እኔ!

**ፈረደ** ታዲያ ከሞትህ መቼ ነው ከመቃብር የተነሣኸው ?

**ምትኩ** (በንዴት) እንዴት እንደዚህ ትጠይቃለህ ?

**ጉርፉ** ምን አለ ረጋ ብላችሁ ስላገራችሁ ሁኔታ ብትወያዩ ?

**ምትኩ** (በከፍተኛ ቍጣ) ባካ ዚምበል ! ዛሬ አንተኖ ያዋረደ ። እኔ ከማን ጋር ኖ ምወያይ? ከዚህ ከአንገርጋሪ ቀበናይ ፤ ከዚ ያገር ሺክማዊ — ፀረ — መሰናከል ሁሉ ጋር ?

**ፈረደ** ለመሆኑ አሁን ምን ይሁን ነው የምትለው?

**ምትኩ** እንዴት ከናንተ ጋር ተወያይ ይለኛል ?

**ተዘራ** (በጉራ እየፎገላ) ለሁሉስ እናንተን ምን አገባችሁ? ተማሪንም ቢሆን የቀሰቀስሁ እኔ! ሠራተኛን የቀሰቀስሁ እኔ ! የተሰደዱትን ሁሉ ተሰደዱ ያልሁ እኔ ! ወታደሩን ያነቃሁ እኔ ! ኧረ እናንተ ምን ሠራን ነው የምትሉት?

**ምትኩ** እንዴት ? በተማሪና በሠራተኛ ደሞ እናንተ አድኻሪ ! ምን አገባችሁ ? እኛ ባለቅን እኛ በተጨፈጨፍን እንደ ቅጠል በረገፍን!

**ፈረደ** አባትህ እዚህ እየገፈፈ በሚልክልህና ለገፉፊ ልጆች እጅግ ለጋስ የሆነ አንድ የምዕራብ



አውሮፓ መንግሥት በሚሰጥህ ገንዘብ የፈረንጅ ምግብና መጠጥ ከነሸርሙጣቸው ስታጣጥም ኢትዮጵያ ውስጥ የተተኮሰ ጥይት የት አግኝቶ ነው ያረገፈህ ?

**ምትኩ** በፊት ማጥፋት እናንተን ነበር ። ደሞ ከእሥራት መፍታት! ማረድ ነበር ። እንደበግ እንደ ፍየል ፤ እንደ ዶሮ ። ደሞ እናንተን የፖለቲካ ሰው ብሎ መቍጠርና ከሥር ቤት መፍታት! እኛ ታግለን እኛ ብቻ የጣልነው መንግሥት የሠራው አንድ ጥሩ ነገር ቢኖር እንደናንተ ያለውን መኸገራዊ — ጸረ መዝለል ። በአልባባዊ ሰቀ — ልጓም ሰንጎ መያዙ ነበር ። አለመፍጀቱ ብቻ ጸረ — ነጽሮታዊ ግዙፍ ስኅተት ነው ።

**ፈረደ** (በንቀትና በርጋታ) እሳ! ጮሌ ፈርጣጭ የፈርጣጭ ልጅ! የኢትዮጵያ ሕዝብ ከኢጣሊያ ፋሽስት ጋር አምስት ዓመት ሙሉ እየተፋጀ ሲቆይ ያ ጮሌ አባትህ የንጉሡን ፈለግ ተከትሎ ወደ አውሮጳ ፈርጥጦ ቆየና አገር ሰላም ሲሆን ልክ እንዳንተ ጕፈሬውን አሳድጎ ከተፍ አለ ። ከዚያም ስንት ዐዋቂ ስንት ጀግና ምንም ሳያገኝ በማዕረግ ላይ ማዕረግ በሥልጣን ላይ ሥልጣን በሀብት ላይ ሀብት ሲደራርብ ፣ አንድ ሙያ ሳያሳይ ታላቅ ግብር በተበላ ቍጥር ሲሸለመው በኖረ መዳሊያና ኒሻን እንደ ቃልቻ በቅሎ ሲዝጕረጕር ኑሮ ይሀን

ሁሉ ጉድ ሳያይ ያው መሰሎቹን የፈጀ የደም ብዛት በሽታ ገላገለው ።

ምትኩ (በከፍተኛ ቊጣ) አድኃሪያን!

ፈረደ ማደሪያ ያሳጣህና ! አሁን አንተ ደሞ የጮሌ ልጅ ጮሌ! አባትህ በኖረበት ዘመን አለመኖርህን ዐውቀህ አባትህ ይኖር በነበረበት መንገድ እንደማያዋጣህ አመዛዝነህ የአባትህን የግፍ ወንበር በአዲስ ዘዴ ለመውረስ በዕድገት የበግ ቆዳ የተሸፈነ ተኩላ ምኞትህን ይዘህ መጣህ ። ለመሆኑ የእኛ ልጆች የሀገራቸውን ሕዝብ ሥቃይና መከራ በቅርብ እያዩ በመቆጨት ብዙዎች ስለተጐዱ በነሱ የደም ዋጋ አንተ እንድ ትካስ ማን ወከለህ? ለሀገራቸው በሞቱ ሰዎች ደም ሁሉ መክካስ ያለባት እናት አገራቸው እንጂ አንዳንድ ጮሌዎች አይደሉም ።

ምትኩ የማይገባህ ቀባጣሪ !

ፈረደ ቆይ እኮ ጉድህን ስማ ።
እኒያ እንዳባትህ ጮሌ የሆኑ የአባትህ ጌታ ከለንደን ሲመለሱ ለንደን ሁነን ኢትዮጵያ ውስጥ ጦርነቱን እንመራ ነበር አሉ ። (በፈገግታ ወደ ጐርፉ ይዞርና) እነ አቶ ጐርፉም ትንሽ ፍንጭ ሲያገኙ ፤ ሲመስላቸው መልአክ ያለዚያም ሰይጣን ማድረጉን ያውቁበታል ፤ ጃንሆይ በጭንቀት በሽብርና በጥቃት ላይ ያለ ሕዝባቸውን በመሐሉ ተገኝተው በማፅናናት ፈንታ ትተዉት ሸሹ ማለት ሲገባቸው ከመጀመሪያው ጦርነቱን በግልጽ ከማድረግ በደፈጣ እናድርገው ብለው ብዙ ሰዎች የመከሯቸውን ምክር ያልተቀበሉትን አጉል የጦር መሪ አርበኞቻቸው በዱር በገደሉ ተሠማርተው ጠላትን እንዲያስጨንቁ ትእዛዝ ሰጥተው የዓለም መንግሥታትን ርዳታ ይዘው ለመመለስ ወደ አውሮጳ ሔዱ አሉ ልን ።

ጐርፉ ጀረ እሳቸው በተመለሱበት ዘመን ነው የተወለድሁ ፤ ከምኑም አልደረስሁ ጌታዬ!

ፈረደ (በቀልድ) ከደረስህ ወዲህ ከዋሸህላቸው ስ ያው አይደል ። የኛ ዶክተር ደግሞ ከአባቱና ከአባቱ ጌታ በለመደው ዘዴ ለመጠቀም የኢትዮጵያ ሕዝብ የቁም ሥቃዩን ሲያይ በምዕራብ አውሮፓ ከተሞች ሲምላቀቅ ቆይቶ አሁን በኢትዮጵያ ሕዝብ ደም ዋጋ አባቱ በማጭበርበር ይዞት የቆየውን ወንበር ሊወርስ ይጣደፋል ። ተምሬያለሁ ካልህ ሒድ ከተራ ሥራ ጀምረህ ሕዝብን አገልግል ። ጣሊያን ሠርቶት አባትህ በጮሌነት ወርሶት በቆየ ምቹ ቤት ውስጥ አዲስ አበባ ተወልደህ ፤ አባትህ ከኢትዮጵያ ሕዝብ በዘረፈው ሀብትና የሀገሩን ጥቅም ለባዕድ በመሸጥ ባገኘው ሽር

ክና በአሥር ዓመትህ በተሰጠህ እስኮላር ሽፕ በውሪነትህ ውጭ አገር ሒደህ የኢትዮጵያ ሕዝብ ተማሪና ወታደር በአንድ ላይ ተነሥቶ ያገኘውን ድል ብቻህን መፈንጫ ልታደርግ አትችልም ።

ምትኩ — መድኃኒቱ አንተን ማረድ ነው ፤ አንተ አድኃሪ!

ፈረደ — ኸረ ለመሆኑ አስተሳሰብህ ምንድን ነው?

ምትኩ — የኔ ነጽሮተ — ግሎብ መፈንድቃዊ — ቅማሬ እንዳንተ ላለ ደንቆሮ አድኃሪ የሚገባው አይደለም ። እኔ በንጽረ - መቋሚያዬ የማ ምነው በማርክሲዝም ሌኒኒዝም ፍልስፍና ነው ።

ፈረደ — የለም ያንተ ፍልስፍና እንደሚገባኝ ማር ክሲዝም አይደለም ።

ምትኩ — አድኃሪ አልገባህም በርግጥ ።

ፈረደ — ገብቶኛል ። ፍልስፍናህ ጥቅምህን ማሳደድ ነው ።

ምትኩ — (በቍጣ ገንፍሎ) አንት አራጅ ያጣህ አድ ኃሪ! ውዳጁ አባቴ አምበርብር ይሙት ራቅ አርድኻለሁ ።

ፈረደ — (ከዘራውን እያስማማ) ሌባ የሌባ ልጅ! ካላረፍህ በዚህ ከዘራ አበራይኻለሁ ። ደሞ አባት ተገኝቶ አምበርብር ይሙት !

ምትኩ — እኔ በቦክስ አልነፋህ መሰለህ ?

ፈረደ — ኸረ ይኸን ምናምንቴ የምናምንቴ ልጅ ገላግሉኝ ! ወይ ጉድ !

ተዘራ — እኔ ሁላችሁም ረፉ ብያለሁ ። አዝዣለሁ ፤ ዝም በሉ!

ጐርፉ — እባክዎ ጌታዬ ቀስ ብለን እንገላግላቸው ።

ምትኩ — ይኸ ሌላ ጸረ - መሰግር ዘካርያስ ደሞ የማን ጉረኛ ኖ !

ተዘራ — ለፈደድ ! እኔ ተዘራ አሳይኻለሁ ። አሁን ፓርቲዬ ስትቋቋም ሁልሽንም ትንፍሽ አላስደርግሽ ።

ምትኩ — (በንዴት) አንተ ብሎ ባለፓርቲ!

ጐርፉ — ኸረ እባካችሁ ረጋ በሉ ።

ምትኩ — (ወደ ተዘራና ወደ ፈረደ በንቀት እያመለ ከተ) ከነዚህ ከነዚህ ጋር ነው በፖለቲካ መስክ የምካፈለው ?

ፈረደ — ኸረ ይህ አጭበርባሪ ያጭበርባሪ ልጅ! አሁን በቃ! ግፍ ጭቆና ረኃብ ውርደት መታፈን በሽታ ድንቁርና ጉስቁልና በነ ሱም ስም እየተጭበረበርን ወደ ባርነት መግባት በቃን ! የማጭበርበሪያ ከፍተኛ ትምህርት የማጭበርበሪያ ጕፈሬ የማጭ በርበሪያ ስብከት በቃን! ከእንግዲህ ወዲህ የኢትዮጵያ ሕዝብ በጮሌነት አይደለ ልም ።

ምትኩ — አድኃሪ ሁሉ!

ፈረደ — አንት ያባቱ ልጅ ! በከዘራ ሳልለምጥህ ዝም ብትል ይሻላል ።

ምትኩ — እስኪ አንተ ደንቆሮ ሽማግሌ ንካኝ ! (ትክ ሻውን ወደ ፈረደ አዞሮ ቀረብ ይላል ።)

ፈረደ — ኸረ ይኸ አበሻ ያላሳደገው የሌባ ልጅ! እፈራው መሰለው ? (ትከሻውን በከዘራው ይነርተዋል ።
ምትኩ ፈረደን በቍጣ ዘሎ ለመያዝ ሲሞ ክር ከበደችና ጕርፉ ይይዙታል ።)

ጕርፉ — ምነው ምን ነካህ ዶክተር?

ምትኩ — ይህን ታማሚ ሽማግሌ አንቀዋለሁ ።

ፈረደ — (ከዘራውን እያስማማ) ና ! ትደገማለህ ።

ጕርፉ — ምነው ጌታዬ ትንሽ ቢታገሡ!

ፈረደ — እኔን እንዳሻው ቢሰድበኝ ምን ቸገረኝ? እሱ የሚለው እኮ ኢትዮጵያን እኔ ብቻ እን ደገና እፈጥራታለሁ ነው ።

ምትኩ — ደንቆሮ! ታዲያ ማን ሊፈጥራት ኑሯል ?

ፈረደ — (በከፍተኛ ቍጣ) አይ አንቺ ያልታደልሽ አገር ! የኢጣሊያ ፋሽስቶች ጠፍተውላት በአዲስ መንፈስ በአዲስ ሥርዓት ተደራ ጅታ ከትክክለኛ ግቧ ትደርሳለች ስንል ጮሌ ጮሌው ጕፈሬ እየተሻማ ካናቷ ላይ ወጣና ፴፫ ዓመት ሙሉ ፈነጨባት ። አሁን ሊፈ ንጭበትና ግራ ሊያጋባት የሚሻው ደግሞ ሌላው ዓይነት ጮሌ ጕፈሬ! የአንድ አገር



ሕዝብ ተባብሮና ተፋቅሮ የጋራ መብቱን ነፃነቱንና መሠረታዊ ጥቅሞቹን ማዳበርና ማበልጸግ ሲገባው እንዴት ከጠቅላላው ማኅ በር መካከል የወጡ ጭብጥ የማይሞሉ ጮሌዎች ይፈንጩበት?

ምትኩ — ገረደማዊ ግርድምድም ደሽርሽራዊ ደነ ኳር ሽማግሌ እኛ በሞትን አንተን ከሱ ታፊያዊ ብሔረ - አንቃዕድዎ ምን ሥረ- ሰነቀር አደረገህ ?

ፈረደ — ደንቆሮ ተብታባ ! መጀመሪያ የምትናገረ ውን ነገር ራስህ ዕወቀው ። አንተ ብሎ የኢ ትዮጵያን ሕዝብ ዐዋቂና ለኢትዮጵያ ሟች!

ምትኩ — (በታላቅ ጩኸት) ተማሪ ለኢትዮጵያ አል ሞተም?

ፈረደ — በምዕራብ አውሮፓ ታላላቅ ከተሞች ስት ንሸራሸር ተማሪዎች ሲሞቱ የኢትዮጵያ ሕዝብ ሲሠቃይ እንዴት ታየህ? በቴሌስ ኮፕ ነው ያየኸው?

ምትኩ — ኸረ ይኸ ዕፍረተ - ቢስ! እንደተማሪ ለሀገሬ ታገልሁ ሊል ነው?

ፈረደ — ዝም በል! ቀጣፊ ጉረኛ ! አሁን በተማሪ ስም ዘሎ ሥልጣን ለማነቅ ነው? አዎ የሀ ገራችንን ወደ ኋላ መቅረትና የወገኖቻች ውን የሥቃይ ኑሮ በቅርብ እያዩ ለመታገሥ ስላልቻሉ ከልብ ይታገሉ ከነበሩ ተማሮች መካከል ብዙ ሙተዋል ፤ ብዙም ተጉላልተ

ዋል ። ሁኖም እነሱ ብቻ አልተጉላሉም ። የብዙ ክፍላተ-ሀገሮች ሕዝብ ያለውን የጭቆና አገዛዝ ሲቃወም ተደብድቧል ። እጅግ ብዙ ነፍስ ከተራው ገበሬ መካከል ጠፍቷል ። አለሁ አለሁ ባዮች ያዳመቁት የጋራ ድርጅት ያልነበራቸው ብዙ የሀገር ተቆርቋሪዎች በአንድ በሁለት እየታደኑ ፣ ጠፍተዋል ። ወታደሩ በጠላትህ ላይ ተኩሰህ ስማችንን አታጥፋ እየተባለ በየጠረፉ በጠላት ጥይት እንዲደበደብ ከመሆኑ በላይ ለኢትዮጵያ ሕዝብ ደኅንነት በየጊዜው ሙቷል ።

ምትኩ ወታደር ? ገዳይስ ማን ነበር ?

ፈረደ እሳ ! የውሻ ልጅ ! አባትህ ተብትቦ ተብትቦ ያስፈቀደውን ትእዛዝ ፈጽም ሲባል ሲፈጽም ኖረ ! የናንተ ምኞት መቼ ጠፋንና ! ተማሪ በዕድሜው ወጣትና የትምህርት ጮራ ያየ ከመሆኑ በላይ አንድ ዓይነት ድርጅት ስላለው ፤ ሠራተኛም እንዲሁ የተደራጀ ስለሆነ አንዳንድ የአንተ ቢጤ ወስላታ የነሱን ስምና ጉልበት የማታለያ መሣሪያ በማድረግ ከሕዝብ እናት ላይ ዘሎ ወጥቶ በቆራጭ ፈላጭነት ለመጨፈር ነው ። ግን ይኸ የሕልም ዳቦ ነው ። ሥልጣን የሕዝብ እንጂ የማንም የግል ሀብት አይደለም ።



ምትኩ አንተ መሰግረ—ምስግርግር ተመነዋዊ ድንካር ኢግሉጽ ባልሆንልህ ነጸብርቆተ—ልዕልናና በማያገባህ ፍላጸዊ ፍንጣሮት አድርገህ ባትዛክር ምን አለበት?

ጉርፉ (ወደ ከበደች ዞሮ) ወይ ጉድ ! ምን ዓይነት ችግር ነው እባካችሁ !

ፈረደ እናንተ እኮ ናችሁ ይኸን ወሽካታ ሁሉ እያስቀባጠራችሁ ሕዝቡን ግራ የምታጋቡት ።

ጉርፉ እኛ ምን አጠፋን ?

ፈረደ ተወኝ ! ተወኝ ! በናንተ ቤት ለፍላፊ ብቻ ነው ሰው የተባለው! ለሀገሬ ታገልሁ የሚል ሁሉ ሀገሩ ከግፍ አገዛዝ ነፃ ስትወጣ ይህን ከፍተኛ ካሣ አድርጎ ማየት ይገባው ነበር። በእነ ምትኩ የተያዘው ጉዳይ ግን ለሀገሬ ስል እንጀራ ስለበላሁና ዊስኪ ስለጠጣሁ መሪነቱ ለእኔ ይገባል ማለት ሆነ ። ነፃነት እኩል የመሥራት የመማር የማደግ ዕድል የሚፈልግ ሕዝብ እንዴት ሲጭበረበር ይኑር?

ጉርፉ እባክዎ አቶ ፈረደ ንዴቱን ይተዉትና እንደ ዐረፍ ይበሉ ። (ስልክ ይደውላል ። ያነሣዋል ።) ወይ መከራ! አሎ! አሎ! ማን ልበል ? የለንም ዘግተናል ። (ስልኩን ይዘጋዋል ። ሴቷ ጋዜጠኛ ፀሐይነሽ ከጉርፉ ቢሮ ፊት ለፊት ክፍቱን ከቆየው ቢሮዋ በቍጣ እየተነቀነቀች በድንገት ትመጣለች ።)

ፀሐይነሽ (ልክ እንዳበደ ሰው ሁና እየተንቀጠቀጠች) ሁላችሁም ብትሆኑ ጨቋኞች ናችሁ!

ጐርፉ ምን ነካሽ ፀሐይነሽ?

ፀሐይነሽ አንተማ ዋናው ጨቋኝ! ግፈኛ! እስኪ እስ ካሁን ወንዶችን ስለደረሰባቸው ችግር ሁሉ ስትጠይቅ ሴትዮዋን ያልጠየቅካት ለምንድን ነው? ሴት ስለሆነች አይደለም? (ወደ ከበደች ጠጋ ብላ በታላቅ ጩኸት) ተነሽ ጭቁኒት! ተነሽ! ከነዚህ ከአድኃሪ ያን ጋር ምን ትሠሪያለሽ? (ከበደች በድንጋጤ በርግጋ ትነሣለች ።)

ምትኩ ተይ፤ አትበጅ! ለይተሽ ተናገሪ!

ፀሐይነሽ አንተስ ምንድን ነኝ ልትል ነው?

ምትኩ ተራማጅ ምሁር ።

ፀሐይነሽ አይ ተራማጅ! ሁሉም ሴትን ጨቋኝ ነው!

ምትኩ ተይ! አለመሳም ጭቆና አይደለም!

ፀሐይነሽ (ስሜቷ በቀጣ እጅግ ተነክቶና ወደ ጐርፉ ዞራ) ለመሆኑ እሷንስ ስለ ደረሰባት ሥቃይ ለምን አልጠየቅካትም? በባህል በሃይማኖት በፆታ በናት በአባት በባል በወንድም በአስተማሪ ስለተጨቆነች! (ወደ ከበደች በመዞር) ተነሽ! ጭፍልቂት ተነሽ! ብዝብዝት ብርብሪት ተነሽ!

ከበደች (በድንጋጤ ግራ እንደገባት) ተነሥቻለሁኮ!



ፀሐይነሽ ዓለም ተባብሮ የጨቆነሽ ምስኪኒት ተነሽ!

ፈረደ እንዴ! ይኸማ ያለዘመድ ልታስቀሪያት አይደል?

ፀሐይነሽ ምን ዘመድ አላት? ብቸኛ ናት ። ተነሽ ብቸኚት! (ከበደች በድንገት መንሰቅሰቅ ትጀምራለች ።)

ጐርፉ ምነው እመቤቴ የሷን ቃል ስምተው ነው የሚያለቅሱት?

ከበደች (በገርነት) እውነቷን ነው፤ በቅርቤ ምንም ዘመድ የለኝ ።

ጐርፉ ለመሆኑ ባለፈው ጊዜ በፖለቲካ ምክንያት የደረሰብዎት እሥራት ወይም ሌላ ዓይነት ችግር አለ?

ከበደች አዎ! ሦስት ጊዜ ታሥሬያለሁ ።

ጐርፉ አ! ይኸማ እውነትም የሚያሳዝን ነው! ለመሆኑ ለምን ያህል ወራት ወይም ዓመታት ታሠሩ?

ፀሐይነሽ ታሳዝኛለሽ? ይኸው ሴት በመሆኗ ሲንቃት!

ጐርፉ አ አ! እባክሽ ተይ ፀሐይነሽ! (ለከበደች) ለስንት ጊዜ ታሠሩ እመቤቴ?

ከበደች እሱስ ሦስት ጊዜም አንዳንድ ቀን ነው የታሠርኩት ።

ጐርፋ — በምን ምክንያት ነበር የታሠሩት !

ከበደች — በሰዓት እላፊ ነበር ። ሦስት ጊዜም ሠላሣ ሠላሣ ብር ፤ (ታስባለች) አዎ! በመጨረሻው ጊዜ ለማስጠንቀቂያ ተብሎ አምሳ ብር ተቀጥቻለሁ ።

ጐርፋ — ለመሆኑ ሥራዎ ምንድን ነው ?

ከበደች — ረሱኝ እንዴ ? ባለመጠጥ ቤት ነኝ !

ፀሐይነሽ — (በማቋረጥና በጩኸት) ብርጭቆ—አደረች! ገላ—አደረች ! ተነሽ!

ጐርፋ — ምነው ፀሐይነሽ ? ጠይቅ አልሽኝ እየጠየቅሁ ነው እኮ ! (የሷን መልስ ሳይጠብቅ ወደ ከበደች በመዞርና ለማረሳሳት በመሞከር) እሺ ፤ እመቤቴ ! ለመሆኑ በምን ምክንያት ወደዚህ ሥራ ተሠማሩ? ባለቤትዎ አቶ ተዘራ በፖለቲካ ስለ ታሠሩብዎት ነው?

ተዘራ — (በፍርሃትና በችኮላ) እኔን ተወኝ ! የለሁበትም ። (ለራሱ) ብቻ እንዳይልታሠር !

ጐርፋ — (እየሳቀ) እሺ እመቤቴ ። በምን ምክንያት ነው ወደዚህ ሥራ የገቡት?

ፀሐይነሽ — አታስጨንቃት፤እናውቀዋለን ። በተፅዕኖ ነው!

ከበደች — (ራሷን በእምቢታ እየነቀነቀች) እ! እ! ተጥኖ የሚባል ሰውስ አላውቅም ። (ከፀሐይነሽ በቀር ሁሉም ይስቃሉ ።) እውነቴን ነው ! ይኸው የራሴን ቡና ቤት ከከፈትሁ እንኳ (ታስባለች) አምስት ዓመት ሁኖ



ኛል ። ከዚያ በፊትም ብዙ ሰው ዐውቃለሁ ፤ ተጥኖ የሚባል ወዳጅ ግን ትዝ አይለኝም ።
(ሁሉም ፈገግ ይላሉ ።)

ጐርፋ — እባክሽ ፀሐይነሽ ባለጉዳይዋን እንጠይቅ ፤ ታገሽን ።

ፀሐይነሽ — ጨቋኝ ! ጨቋኝ ! (ደረቱን በሁለት ጡጫዎቿ ትመታታዋለች) ግፈኛ ! ሴት በዳይ ! ሴት ናቂ !

ጐርፋ — (እየሳቀ) ጉድ ፈልቶብኝ ! (ቀስ አድርጎ ይገፋታል ።) እሺ እመቤቴ! ታዲያ በምን ምክንያት ወደዚህ ሥራ ገቡ ?

ከበደች — ነገሩ ብዙ ነው በመጀመሪያ ጥፋቱ የኔ ነው ። አባቴ ዳኛ ነበሩ ። ለናት ለአባቴ አንድ ነኝ ። በደንብ ሳያስተምሩ አቅብጠው አሳደጉኝ ። በኋላ ቶሎ ዳሩኝ ።

ፀሐይነሽ — ለማትወደው ሰው ዳሩዋት !

ከበደች — እ! እ! እሱ እንኳ በጣም እወደው ነበር ። ብቻ ተሳሳትሁ ።

ጐርፋ — ምን ጥፋት ሠሩ ? ከሌላ ወንድ ጋር ተያዙ?

ከበደች — ኧረ በስማም ! ከባሌ ላይ ?

ፀሐይነሽ — ብትያዝስ ምን አለበት !

ተዘራ — ኧረ ! ኧረ እች ዕብድ ምኑን አመጣችው ደሞ ።

ፀሐይነሽ — እ! የኛ ብልጦች! እናንተ ብቻ የፈለጋችኋትን . . እ . . እንትን ልትሉ? ጥቂት (ታስባለች) ይህ አድኃሪ ልማድ በግልጽ እንዳልናገር አረገኝኮ! እናንተ ብቻ የፈለጋችኋትን ልትበ . . . (ጐርፉ ዘሎ አፏን ያፍናታል ።)

ተዘራ — ለመሆኑ ጤነኛ ናት?

ፀሐይነሽ — (ጐርፉን ነጥቃ ወደ ተዘራ በመዞርና በመንቀጥቀጥ) አድኃሪ! የሃይማኖት የወግ ተገዥ! ከዕንቅልፍህ ያልነቃህ!

ተዘራ — እሳ! መልክ ከጤና የነሳት ዕብድ!

ፀሐይነሽ — (ወደ ተዘራ ተጠግታ) ጨቋኝ! ጨቋኝ!

ተዘራ — ተይ ባለሽበት ቁሚ ያለዚያ . . . .

ፀሐይነሽ — እስኪ ንካኝ! እስኪ ንካኝ!

ተዘራ — አይ! እኔ አልነካሽም ።

ፀሐይነሽ — ወደህን?

ተዘራ — የለም ጠልቼ ነው ።

ፀሐይነሽ — አንተ ነህ እኔን የምትጠላ? ቀላል ሽማግሌ!

ተዘራ — አዋ! እቺ ዕብድ ዝንጀሮስ ጉድ አፈላች ።

ፀሐይነሽ — ውይ! አንተ ነህ በኔ የምትቀልደው?

ተዘራ — የቀለደብሽ አውሬ ፊትሽ እንጂ እኔ አይደለሁም ።



ፈረደ — ሁላችሁም ብትሆኑ ረጋ በሉ ። ጭቆናና መኖርስ አለባቸው ። እኔ ራሴ ራሴን ሳጋልጥ ውና ሚስቴን በቀበቶ የገረፍኹባቸውና በጥፊ የመታሁባቸው ቀኖች ቍጥር እንኳን ጥቂት አይደለም ። አዎ ፤ መጨቆን አለ ፤ ይገባኛል ። ቢሆንም እውነተኛውን ችግር ተረድተን የሚያዛልቀውን መድኃኒት መፈለግ እንጂ በከንቱ በመጯጯህ ከመሳቂያነት በስተቀር ዘላቂ ዕድል የምናገኝ አይመስለኝም ።

ፀሐይነሽ — ሁልህም አታላይ!

ፈረደ — ኧረ አይደለንም ።

ተዘራ — ተይ ዕረፊ አይሆንም!

ፀሐይነሽ — ቀጣፊ ቀጠፍጣፊ!

ተዘራ — በይ ይሁንልሽ ። አሁን አንቺን ምን ልልሽ ነው? እግዜር የጐዳሽ ይበቃሻል ። (ፈረደ ለመውጣት ጉዞ ይጀመራል ። ፀሐይነሽ የንዴት ዕንባ እየተናነቃት ወደ ክፍሏ ለመሔድ ትጀምራለች ።)

ጐርፉ — ቆዪ እንጂ ፀሐይነሽ እኔ አልነካሁሽ!

ፀሐይነሽ — አንተም ብትሆን ዋሾ ነህ!

ጐርፉ — (በራሱ ቀልድ እየሳቀ አዋ! ከብት ናት? ታዲያ ሥራዬን ልተውልሽ ነው! ይልቅስ ቀልዱን ተዪውና ነይ!

ፀሐይነሽ — ከብት ራስህ! ደሞ ሰውን ከብት ይላል ። (ወደ ውጭ ትሔዳለች ።)

ተዘራ	ግን እኮ እውነትም ሁላችንም ቀዳዶች ነን ።

ፈረደ	መጠርጠሩስ !

ተዘራ	ውሸቱንስ አንዋሽ! ግን በማን ላይ? በሀገራችን ?

ፈረደ	በሰው ሀገርማ እንኳንስ ለኩሸት ለኑሮም ችግር አለ ።

ተዘራ	ኤድያ! እንኳን ዋሸሁ! በገዛ ሀገሬ ያልዋሸሁ የት ሔጄ ልዋሽ? ደግ አደረግሁ!

ፈረደ	(ለገበሬው) ጉድ! በል ወንድሜ ደኅና ዋል ። እኛ መቼም ልንረዳህ ሳይሆን በጩኸት ልናደርቅህ ነው የተፈጠርነው ። (የባላገሩን እጅ ይጨብጣል ። ወደ ጋዜጠኛው ይዞራል ።) አቶ ጉርፉ ተዉ! ጥቂት ጥቂት ኀሊና ይኑረን! እናንተ ለምትወዷቸው ሰዎች ብቻ መጨፈሪያ አታድርጉን! አሁን ለዚህ ደሀ ገበሬ ዕድል ሰጠነው ? በርሱ ስም ስለ ርሱ እንናገራለን ። ግን ከልብ አንወደውም ።

ጉርፉ	ይተዉ እያሳጡን ። ይኸማ ቅሌት ነው ።

ፈረደ	(በታላቅ ቍጣ) ቅሌት? ቅሌታምሰ ራስህ ። ድሮስ የነተዘራ ጓደኛ ምን ልትሠራ? ዋሾ! (ይወጣል ።)

ምትኩ	እኔስ ለለውጡ ጓጉቼ መጥቼ አይደል እዚህ የማንም ጉምብርግር መውገርገሪያ የሆንሁት! (ይወጣል ።)

ጉርፉ	አይ የኛ ዶክተር! ቀዳዳ ውዥግርግር!



ተዘራ	እኔኮ! ቅድሙን ሁላችንም ያው ነን ብያለሁ ። ቅድም አላልኳችሁም? በይ ከብዬ! መኪና ውስጥ እጠብቅሻለሁ! እዚህ ከማንም ውንግርግር ጋር! (ይወጣል ።)

ጉርፉ	(ወደከበደች ከውሸት ፈገግታ ጋር ዘወር ብሎ) ዐየሽ ይኸን ሁሉ ውሸት? የውልሽ ይህን ሁሉ ችለን ነው የምንኖረው ።

ከበደች	(በቍጣ እየተነሣች) አንተ ! አንተስ አላሳፍርህም ብዬ እንጂ በዕለተ-መባቻ በጠዋቱ ዋሽተህልኝ የሔድኸውን ስጦታ መች አመጣህልኝ ? ጥሩንባ!

ጉርፉ	አድዮ! እውነት ከነመዋደድ ! ምነው ከብዬ አለወትሮሽ ልብሽ ጨከነ? (ከበደች ትወጣለች ። ለብቻው ተከዝ ብሎ ይቆያል ። ከዚያም ተነሥቶ ወደ በር ጉዞውን ይጀምራል ።)

ባላገር	(ወረቀቱን እያቀረበ) ጌታዬ! የኔው ጉዳይ ተረሣኮ!

ጉርፉ	ዝም በለኝ ሥራ-ፈት! (ትቶት ይወጣል ። ገበሬውም ወረቀቱን ቀዶ ይወጣል ።)

ተፈጸመ ።